# ኅብረት ሥራ

# COOPERATIVE



በፌደራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ የህዝብ ግንኙነት ዳይሬክቶሬት እየታተመ የሚወጣ ዓመታዊ መጽሄት

Annual Publication of the Federal Cooperatives Agency Public Relation Directorate

ሰኔ 2005 ዓ.ም. ቅጽ 10 ቁጥር 1 / volume 10 No. 1
















## የኅብረት ሥራ ማህበራት የቀውስ ወቅትን ይቋቋማሉ!

## *Cooperative enterprises remain strong in time of crisis.*

በፌደራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ የሕዝብ ግንኙነት ዳይሬክቶሬት




**የተደራጀ የኅብረት ሥራ ልማት ሠራዊት በመገንባት የመሪያችንን ራእይ እናሳካ!**

## አገራዊ ራእይ

**በህዝቦች ተሳትፎና መፈቃቀድ ላይ የተመሰረተ ዴሞክራሲያዊ ስርአትና መልካም አስተዳደር የሰፈነባት ፤ማህበራዊ ፍትህ የነገሰባት ከድህነት ተላቃ መካከለኛ ገቢ ያላት ኢትዮጵያን እውን ማድረግ ነው።**

## የፌዴራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ ተልዕኮና ራዕይ

### ተልዕኮ

በገጠርና በከተማ የሚኖረው ሕብረተሰብ የአካባቢውን ሀብት መሠረት አድርጎ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ችግሩን ለመፍታት በፈቃደኝነት ላይ ተመስርቶ በተለያየ ዓይነትና ደረጃ የኅብረት ሥራ ማህበራትን በማደራጀት፣ አቅማቸውን በመገንባት የገበያ ድርሻቸውን በማሣደግ በህግና ደንብ እንዲመሩ በማድረግ የአባላትን ተጠቃሚነት ያረጋገጡ የህብረት ሥራ ማህበራትን መፍጠር።

### ራዕይ

በ2015 ዓ.ም የአባላትን ኑሮ ያሻሻሉና በአገሪቱ ኢኮኖሚ ግንባታ የላቀ ሚና ያላቸው ኅብረት ሥራ ማህበራት ተፈጥረው ማየት።

# ኅብረት ሥራ
# COOPERATIVE

## ማውጫ

ርዕስ ገጽ




**አዘጋጆች**
ደግዛው ዳኘው
ጫልቱ ታምሩ
አበራ በቀለ
ምልኪ ሰፈራ

**የምስል ቅንብር**
ሀብታሙ ወንድሙ

**ኤዲተር**
ኃይሉ ዘለቀ

**የኮምፒዩተር ጽሑፍ**
ስንታየሁ ጌታቸው



በፌደራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ የሕዝብ ግንኙነት ዳይሬክተሬት

ኢ- ሜይል fcoopapr@yahoo.com ስልክ 0118 96 36 84 ወይም 0118 59 22 74

# የዝግጅት ክፍሉ መልእክት

# እያንዳንዱ ቀን ታሪካዊ ቀን ነው

እስከ ዛሬ የተጓዝንበትን መንገድ ወደኋላ መለስ ብለን ብንቃኝ ለትውልድ ቅርስ የሚሆኑ በርካታ እውነቶች፣ ሥራዎችና ሁነቶች እናገኛለን። የለውጥ ሀሳብ፣ የነፃነት ንቅናቄ የፈለቀበት፣ የትጥቅ ትግል የተጀመረበት፣ የታላላቅ የልማት መሰረት ድንጋይ የኖረበት፣ ለውጤት የበቁ እልህ አስጨራሽ ድሎች የተመዘገቡት ሁሉ ከቀናቱ በአንዱ ቀን ነው። ሁሉም ቀን የራሱ ታሪክ አለውና።

እያንዳንዱ ቀን በራሱም ዕድልና ወቅት የድርሻው እንዲከፈልለት ለባለታሪኩ ቀን መሸብረቅ የራሱን ድርሻ ይሰዋል። ባለታሪክ ለመባል በተሰለፍንበት ሞያ በተሰጠን ኃላፊነት የምንሠራው ሥራ አሽቶ ጎምርቶ በብዙሃን ዓይን ገብቶ አርክቶ በታሪክነት እንዲመዘገብ የየቀኑን ድርሻ መጠን መክፈል ይጠበቅብናል። ለሚመጣው መልካም ውጤት የዛሬ መስዋእት መክፈል አለበትና።

በየቀኑ መወጣት ያለብንን ኃላፊነት ባንወጣ ለነገው ሥራ ስኬትና የምንጠብቀው ታሪክ ጎዶሎ ይሆናልና። በድንገት እድለኛው ቀን ዛሬ ሆኖ በታሪካዊነት ቢመዘገብ ታሪኩ የኋልዮሽ ሲለካ በጎደለው ሚዛን ከመመዘን በታለቁ እድለኛው ቀን ሙሉ ሆነን እንገኝ።

የዘረፉን ታሪክ መሠረት ለማስያዝ መንግስት የህብረትሥራ ማህበራት ለኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ እድገት ያላቸዉን አስተዋጽኦ በመገንዘብ ጠንክራ፣ ዘላቂና ዉጤታማ የህብረትሥራ እንቅስቃሴ እንዲኖር ባለው ቁርጠኝነት የፌደራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ ተቋቁሞ እንቅስቃሴ እያደረገ ይገኛል። እንዲሁም የኅብረት ሥራ ማኅበራት ይበልጥ የአባሎቻቸውን ተጠቃሚነትና የአነስተኛ አርሶአደሮችን ምርታማነትና ገቢ ለማሳደግ እንዲቻል የአምስት ዓመት የግብርና ህብረት ሥራ ዘርፍ ልማት ስትራቴጂ /2004-2008/ ተቀርፆ በመተግበር ላይ ነው።

ይህንንም ተግባር ለማጠናከር በልማታዊ የኮሙኒኬሽን ዘዴዎች በመደገፍ አቅዶችን ለማስፈፀምና መረጃዎችን ለሕብረተሰቡ ለማድረስ ለታሪካዊው ቀን ማሟያ እየሠራን እንገኛለን።

ዉድ አንባቢዎቻችን ወቅታዊ መረጃን ለማስተላለፍ ከምንጠቀምባቸዉ የህትመት ዉጤቶቻችን በተጨማሪ የዘርፉን ሥራች ለህብረተሰባችን ለማድረስና እንዲተላለፍ ለማድረግ በሳምንት አንድ ቀን ማክሰኞ ማታ ከ1፤40 ጀምሮ የሚተላለፍ የሬዲዮ ፕሮግራም በፋና ብሮድካስቲንግ ኮርፖሬት ሀገራዊ ስርጭት በማስራጨት ላይ እንገኛለን።

አስረኛ ዓመቷን የምታስቆጥረዉ መጽሄታችን በዓለም ለ91ኛ ጊዜ በተባበሩት መንግስታት ለ19ኛ ጊዜ በሀገራችን ለአምስተኛ ጊዜ የሚከበረዉን በዓል ምክንያት በማድረግ ዘርፈ ብዙ ጉዳዮችን አካታ ወደ እናንተ መጥታለች። መጽሄቷም በዋና ዳይሬክተር መልእክት በማስቀደም የግብርና ህብረት ሥራ ዘርፍ ልማት ስትራቴጅ በትኩረት አምድ በማስከተል እነሆ እንላለን።

ዉድ የመጽሄታችን አንባቢያን ለወደፊቱ ሥራችን መሳከት የእናንተ አስተያየት አስፈላጊ መሆኑን እናምናለን በመሆኑም በአድራሻችን አስተያየታችሁን እንድትልኩልን በአጽንኦ እንሻለን።

መልካም ንባብ!!!

# መልዕክት



ክቡር አቶ ኡስማን ሱሩር
የፌዴራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ ዋና ዳይሬክተር

ሀገራችን የምትታወቅበትን የድህነትና ኋላ-ቀርነት ገፅታ ለመቀየር እና በሂደቱም የሀገራችን ሕዝቦች ተሳታፊነት እና ተጠቃሚነት ደረጃ በደረጃ ለማረጋገጥ በተቀየሱ የሰላም፣ የልማትና የዲሞክራሲ ስርዓት ግንባታ ፖሊሲዎች፣ ስትራቴጂዎች እና ስልቶች ተጨባጭ ውጤቶችን ማስመዝገብ ጀምረናል።

አሁን ለደረስንበት የዕድገት ደረጃ እና በቀጣይም ረጅም ርቀት እንደሚያስጉዙን በተግበር ተሞክረው በተረጋገጡት በእነዚህ ፖሊሲዎች፣ ስትራቴጂዎች እና ስልቶች የታላቁ ባለ-ራዕይ መሪያችን የቀድሞው ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር መለስ ዜናዊ ድርሻ ተከ. የሌለው ነው። እነዚህ ትክክለኛ የማስፈፀሚያ መሳሪያዎች ሀገራችንን በማይገታ ፈጣን የዕድገት መሠላል እንድትወጣ ያስቻሉዋት መሆኑ የሁሉንም ወገን አወንታ አስገኝቷል። በአብዛኛው የዓለም ሀገራት እንደሚታየው የህብረት ስራ ማህበራት ዕድገትን ወደ ላቀ ደረጃ ለማሸጋገር እና የኢኮኖሚ ቀውስንና የልማት ማነቆዎችን ለመቋቋም ከሚሰለፉ የልማት ኃይሎች መካከል መተኪያ የሌላቸው ተቋሞች እንደሆኑ ማስመስከር ችለዋል። በሀገራችን የተጀመረውን ዕድገት ወደ ላቀ ደረጃ ለማሸጋገር ከተሰለፉ የልማት ኃይሎች መካከልም የኅብረተሰቡ ጠንካራ ኢኮኖሚያዊና ማኅበራዊ ተቋም የሆኑት የኅብረት ሥራ ማኅበራት መሆናቸው ሊሰመርበት የሚገባ ጉዳይ ነው።

በመሆኑም የሀገራችን የኅብረት ሥራ ማህበራት አደረጃጀት የዓለም አቀፍ የኅብረት ሥራ እሴቶችንና መርሆዎችን እንዲያጣትቱ እንዲሁም የኅብረት ሥራ ማህበራት ከየተሰማሩበት ስራ አንፃር የተገናዘቡ ውጤታማ ልምዶችን እንዲቀስሙ በተረደገው ጥረት የዜጎች የግንዛቤ ደረጃ በማደጉ ከ6.5 ሚሊዮን በላይ አባላትን ያቀፉ ከ43 ሺ በላይ መሠረታዊ የህብረት ስራ ማህበራትና ከ1.5 ቢሊየን በላይ ካፒታል ያፈሩ እንዲሁም ከ293 በላይ ሁለተኛ ደረጃ የኅብረት ሥራ ማኅበራት (የህብረት ስራ ዩኒየኖች) ተቋቁመው የአባላትንና የአካባቢያቸውን ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ችግሮች እየፈቱ ይገኛሉ።

የህብረት ስራ ማህበራት የአርሶ አደሩንና አርብቶ አደሩን ምርትና ምርታማነት ለማሣደግ የተሻሻሉ ቴክኖሎጂዎች፣ ግብዓቶችና አሠራሮችን ወደ ሁሉም ተጠቃሚዎች በማድረስ የህብረተሰቡን ተጠቃሚነት በማረጋገጥ ረገድ የድርሻቸውን በመወጣት ላይ ይገኛሉ። በቴክኖሎጂ ሽግግር የተገኘው የግብርና ምርት ዕድገት ገበያ በማጣት ወደኋላ እንዳይመለስ አምራቹ አርሶና አርብቶ አደር ከምርቱ ፍትሃዊና ተመጣጣኝ ዋጋ ተቀባይ ብቻ ሳይሆን የገበያ ዋጋንም መወሰን እንዲችል በነፃ ገበያው መርህ የመደራደር አቅሙ እንዲጐለብት ለተሻለ የልማት ሥራና ምርታማነት እንዲነሳሳ ረድተዋል። በተለይም ለውጭ ገበያ የሚቀርቡ የግብርና ምርቶችን የጥራት ደረጃ እንዲጨምር በማድረግ ከተገኘው ተጨማሪ ገቢ የአባላትን ኑሮ ከማሻሻል ባሻገር የሀገሪቱ የውጭ ምንዛሪ ከፍ እንዲል ጉልህ ሚና ተጫውተዋል። በመጫወትም ላይ ይገኛሉ።

በፋይናንስ ግብይቱ ዘርፍም የኅብረት ሥራ ማኅበራት የፋይናንስ አሠራር ሥርዓት በገጠርና በከተማ እንዲስፋፋ በማድረግ የቁጠባ ባህልን በማጐልበት እና ብድርን ለልማት በማዋል የሥራ ፈጠራዎችን ለማስፋፋት ከማገዛቸውም ባሻገር ለትልቅ ኢንቨስትመንት የሀገር ውስጥ የፋይናንስ ምንጭን በማጐልበት ላይ ይገኛሉ።





በግብርና መር ኢንዱስትሪያላይዜሽን መርሃ ግብራችን በአርሶ አደሩና በአርብቶ አደሩ ምርት ላይ ተጨማሪ እሴት በመጨመር ለዕድገትና ትራንስፎርሜሽን ዕቅዳችን ግብ ስኬት የበኩላቸውን ጥረት በማድረግ ላይ ይገኛሉ:: ከዚህ ጋር በተያያዘ በገጠሪቱ ኢትዮጵያ እስከአሁን የግብርና ምርቶችን የሚያቀነባብሩ ከ54 በላይ አግሮ-ኢንዱስትሪዎች የተቋቋሙ ሲሆን ይህንን ጅምር በሁሉም የኢንዱስትሪ ዘርፎች በማስፋት ለአባላት እና ለአካባቢዉ ህብረተሰብ የሥራ ዕድል መፍጠር ጀምረዋል::

በከተሞች የሚታየውን የኑሮ ውድነት በማረጋጋት ረገድም በተለይም በመሰረታዊ የፍጆታ እቃዎችና ሸቀጦች ላይ የሚመጣውን ያልተገባ የዋጋ ንረት በማረጋጋት ረገድ የሸማቾች ኅብረት ሥራ ማኅበራት ለሸማቹ ኅብረተሰብ አንድ አማራጭ ሆነው አገልግሎት በመስጠት ገበያን የማረጋጋት ስራ እያከናወኑ ይገኛሉ::
ይሁን እንጂ በአምስት ዓመቱ በእመርታዊ ለውጥ ለመሸጋገር ከታቀደው ግዙፍ እቅድ አንፃር በዘርፉ ዘርፈ ብዙ ያልተሸገርናቸው ማነቆዎች አሉ:: ከዘርፉ የሚጠበቀውን ልማት ከዳር ለማድረስ በመንግስት አመራሩ በየደረጃው በሚገኙ አደራጅ መስሪያ ቤቶች በሚሰሩ ፈጻሚዎች፣ በኅብረትሥራ ማኅበራት አመራር አካላት እና አባላት እንዲሁም በህብረተሰቡ የአመለካከትና የግንዛቤ ችግሮች አሁንም ይታያሉ:: በተለይ በህብረት ስራ ማህበራቱ ውስጥ የአደረጃጀት፣ የአመራርና አሠራር ሥርዓት በተገቢው ባለመጠናከሩ ምክንያት ህብረት ስራ ማህበራቱ ለተለያዩ አካላት ለምዝበራ የተጋለጡበት ሁኔታ ይስተዋላል:: በዚህም ምክንያት አልፎ አልፎ በኅብረት ሥራ ማኅበራት ሀብትና ንብረት ምዝበራና ብክነት እና የሥነ-ምግባር ጉድለት መከሰት ለኅብረትሥራ ማኅበራት እድገትም ሆነ በአባሎቻቸው ዘንድ የባለቤትነት ስሜት ለማጣት ቁልፍ ማነቆ ሆኖ ይገኛል::

በመሆኑም ሀገሪቱ የነደፈቻቸውን ዘርፈ ብዙ የልማት ውጥኖች በተለይም የዕድገትና ትራንስፎርሜሽን እቅድ ስኬት እና ሀገሪቱ ወደ መካከለኛ ገቢ ወደላቸው ሀገሮች ተርታ ለመሰለፍ ለምታደርገው ጉዞ ህብረት ስራ ማህበራት መላውን ህብረተሰብ በተደራጀ መንገድ ለማንቀሳቀስ እና የሀገሪቱን ውጥኖች በተቀመጠው አቅጣጫ ለማሳካት አይነተኛ ሚና ያላቸው ተቋማት መሆናቸውን በየደረጃው ያለው አመራርና ባለሙያ በግልጽ ተገንዝቦ አጋዥ ሚናውን እንዲጫወት ማድረግ በቀጣይ የሚጠብቀን ተግባር ይሆናል:: በዚህ ዙሪያ የሚታዩ ችግሮችን ለመፍታት መላ የህብረት ስራ ማህበራት አባላትንና የየአካባቢውን ህብረተሰብ በማሳተፍ የተጀመረውን የህብረት ሥራ ንቅናቄ አጠናክሮ ማስቀጠልና የግብርና ህብረት ሥራ ልማት ስትራቴጂ መተግበር ሌላው በትኩረት የሚፈጸም ተግባር ይሆናል::

በሌላ በኩል ደግሞ በየደረጃው ያለው አመራር በህብረት ሥራ ማህበራት አካባቢ በአመለካከትም ሆነ በተግባር የሚታየውን የኪራይ ሰብሳቢነት ዋሻ በመናድ የአባላትን ተቆጣጣሪነት፣ ባለቤትነትና ተጠቃሚነት የማረጋገጥ ጉዳይ ጊዜ የማይሰጠውና በአጭር ጊዜ መሻገር ያለብን ሥራ ይሆናል:: የህብረት ስራ ማህበራት በአደረጃጀታቸው፣ በአሠራራቸው፣ በአመራራቸውና በኢኮኖሚ ብቃታቸው ተጠናክረው የአርሶ እና አርብቶ አደሩን ወቅታዊ፣ ጥራት ያለውና በተመጣጣኝ ዋጋ የምርት ማሳደጊያ ግብአቶችን ማቅረብና መሰራጨት፣ ለተመረተው ምርት ፍትሃዊና ተመጣጣኝ የገበያ ዋጋ እንዲያገኝ በማድረግ የአባላትን ገቢ ማሳደግ፣ በገጠሩ አካባቢ የሚታየውን የፋይናንስ አቅርቦት ለማሻሻል የአባላትን የቁጠባ ባህል ማዳበር እና አምራቹንና ሸማቹን ባጠረ የግብይት ሰንሰለት በማገናኘት የሁለቱንም ወገኖች ተጠቃሚነት ማረጋገጥና በግብርና ምርቶች ላይ እሴት የመጨመር ጉዳይ መሰረታዊ አቅጣጫችን ይሆናል:: ይህንን ሀገራዊ ሀላፊነታቸውን መወጣት እንዲችሉ ከፌደራል እስከ ቀበሌ ያለው መዋቅራችን የተደራጀ የልማት ሰራዊት ፈጥሮ መንቀሳቀስ ቁልፍና ጊዜ የማይሰጠው ተግባር ይሆናል::

በመጨረሻም በሀገሪቱ የህብረት ስራ ልማት ዕድገት አይነተኛ ሚና የነበራቸውንና ህብረት ስራ ማህበራት ሀገሪቱ ለተያያዘችው የብልጽግና ጉዞ የማይተካ ሚና እንዳላቸው አበክረው ሲያስገነዝቡን የነበሩትንና በድንገት የተለዩንን የሀገራችን የህዳሴ ጉዞ ቀያሽ መሐንዲስ የቀድሞው ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር መለስ ዜናዊ ራዕይ ዕውን ሆኖ እንድናይ በ2015 የአባላትን ኑሮ ያሻሻሉና በሀገር ኢኮኖሚ ግንባታ የላቀ ሚና ያላቸው የኅብረት ሥራ ማኅበራት የማየት ህልማችን እንዲሳካ የዘርፉ ሙያተኞች፣ ማህበራትና ባለድርሻ አካላት በእልህና በወኔ በመንቀሳቀስ የድርሻችንን እንድንወጣ ጥሪዬን አቀርባለሁ::

አመሰግናለሁ::

# ትኩረት

## የግብርናና ኅብረት ሥራ ዘርፍ ልማት ስትራቴጂ ስተገባበርና ቀጣይ ጉዞ

ቅንብር በአበራ በቀለ

ፈጣን ቀጣይና ፍትሀዊ ኢኮኖሚ ማስመዝገብ በአምስት ዓመቱ የዕድገትና ትራንስፎርሜሽን እቅድ የመጀመሪያው ምሰሶ ነው። ዕድገቱን ለማረጋገጥ ደግሞ በዘላቂነት የግብርናውን ምርትና ምርታማነት ማሳደግ የዕቅድ ዘመኑ አበይት ተግባር ነው። የተሻሻሉ ቴክኖሎጂ መጠቀምና ገበያው የሚፈልገውን ምርት ማምረትና ማቅረብ፣ እንዱስትሪውን መደገፍ ይጠበቅበታል። ይህንን ግዙፍ ዕቅድ ለማሳካት በነባሩ የግብርና አሠራር ላይ ስርነቀል ለውጥ ማምጣት ይጠይቃል። ለውጡን ለማምጣትም እስትራቴጂ መንደፍ ቀዳሚ ስራ ነው። ምክንያቱም እስትራተጂ በባለሞያዎቹ ትርጓሜ Strategic planning is longer term orientation and definition of policies, activities and organisational development. This usually affects or takes into account structural and infra-structural changes (or triggers them). ስለሆነ ነው። ግብርናውን ለመለወጥ እንዲሁ የግንባር ቀደም ተዋንያንን አጠቃላይ መሠረታዊ ለውጥ የሚጠይቅ ነው። ከተዋንያኑ አንዱ ደግሞ የግብርና ህብረት ሥራ ዘርፍ ነው። ዘርፉ ለግብርና እድገት አርሶ አደሩ ገበያ መር የሆኑ ምርቶች እንዲያመርትና ለምርቱም ተመጣጣኝ ዋጋ እንዲከፈለው በገጠሩ ውስጥ አስተማማኝ የግብይት ስርዓት መፍጠር ስለሚችል ነው።

የግብርና ህብረት ሥራ አብዛኛው የሀገራችን የሕዝብ ቁጥር ባለበት የገጠሩ አካባቢ የምግብ ዋስትና በማረጋገጥ የነፍስ ወከፍ ገቢን ለማሻሻል ከሚጥሩ አካላት መካከል በቀዳሚነት ይጠቀሳል። ዘረፉ ሀገራችንን ከድህነት ለማላቀቅ በተዘረጋው ፖሊሲና እስትራቴጂ ዋና ተዋናይና ፋና ወጊ ሆኖ ተጫባጭ ለዉጥ እያስመዘገበ ነው። እየተመዘገበ ላለውም የኢኮኖሚ ዕድገት ያበረከተው አስተዋፅኦ በቀላል የሚገመት አይደለም። በቴክኖሎጂ አቅርቦትም ሆነ ለምርቱ ፍትሀዊ ገበያ ለማስገኘትና ገበያው የሚያስገኘውን ትርፍ የምርቱ ባለቤት ተጠቃሚ እንዲሆን ለማድረግ ብዙ ሰርተዋል።

ሆኖም ይህ አስተዋፅኦአቸው ይበልጥ ጎልብቶ ለግብርናው እድገት ቁልፍ ሚናቸውን እንዲጫወቱ ለማስቻል የተጋረጡባቸውን ማነቆዎች እየለዩ በወቅቱ ማቃለል ወሳኝ ጉዳይ ነው። አርሶ አደሩ ገበያ መር የሆኑ ምርቶች እንዲያመርት በገጠሩ ውስጥ አስተማማኝ የግብይት ስርዓት ለመፍጠር እንዲቻል በግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራት ተቋማዊ ብቃት ላይ መሠረታዊ ለውጥ ማምጣት ይጠይቃል። የአምስት ዓመቱ የዕድገትና ትራንስፎርሜሽን ዕቅድም ኅብረት ሥራ ማህበራት በአደረጃጀት፣ በአሠራር ሥርዓታቸውና በሰው ኃይላቸው ይበልጥ ጎልብተው እንዲወጡ ማድረግ ነው። በመጨረሻ የሚለካው ውጤትም የአርሶ/ አርብቶ አደሩ ምርትና ገበያ መሻሻል ይሆናል።

መንግስትም የዘረፉን ጠቀሜታ ለማሻሻል ትልቅ ትኩረት ሰጥቶ በግብርና ኅብረት ሥራ ዘርፍ መሰረታዊ ለውጥ ማምጣት የሚያስችል ስትራቴጂ በግብርና ትራንስፎርሜሽን ኤጀንሲ እንዲዘጋጅ አድርጓል። የግብርና ኅብረት ሥራ ዘርፍ ልማት ቅድሚያ ትኩረት ማግኘቱ ምክንያት የሀገሪቱ ኢኮኖሚ ኢንዴክስ እንደሚያመለክተው The economy of Ethiopia is based on agriculture, which accounts for 46.3% of gross domestic product (GDP), 60% of exports, and 80% of total employment. ግብርና ለኢትዮጵያ ዕድገት መሠረት፣ ለውጭ ምንዛሬውና የአብዛኛው መተዳደሪያ ገቢ ምንጭ ስለሆነ ነው።

የስትራቴጂ ሰነዱ በሙያው ዓለም አቀፍ ተሞክሮ ባላቸው ሙያተኞችና እና በአገራችን የዘርፉ ሙያተኞች በጋራ ተሳተፎፎ እንዲዘጋጅ ተደርጓል። ሰነዱ ዓለም አቀፍና የአገራችን ተሞክሮቸን የዳሰሰና ለግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራት እድገት ዋና ማነቆዎችን የለየና ማነቆውን የሚፈታ ስትራቴጂያዊ የመፍትሄ አቅጣጫ ያስቀመጠ ነው።

ይህ እስተራቴጂ ሊፈታ ያለመው ቁልፍ ጉዳይ እና በትግበራው ምዕራፍ የተገኘውን ውጤት በአጭሩ ለመዳሰስ ተመክሯል፡-

**በስትራተጂው ለመድረስ የተቀመጠው ራዕይ፣-** አገራችን በ2017 መካከለኛ ገቢ ያላት በመሆን ላስቀመጠችው አጠቃላይ አገራዊ ራዕይ በግብርርና ኅብረት ሥራ ማኅበራት አማካኝነት የአነስተኛ አርሶ አደሮችን ምርታማነትንና ገቢ በመጨመር አስተዋፅኦ ማድረግ ሲሆን ተልዕኮውም በርካታ አነስተኛ አርሶ አደሮችን ምርት እና ገቢ ለማሳደግ የሚያግዙ በአግባቡ ተግባሮቹን የሚወጣ የግብርና ኅብረት ሥራ ዘርፍ በመገንባት ሀ) ራስ ገዝ እና ውጤታማ የኅብረት ሥራ ማኅበራት በሁሉም የአደራጃጀት እርከን በማደራጀት ውጤታማና ዘለቄታዊ አገልግሎት ለአባሎቻቸው እንዲሰጡ ማድረግ፣ ለ) የግብርና ኅብረት ሥራ ማኅበራት ውጤታማ እንዲሆኑ የሚያስችል ድጋፍ እንዲያገኙ የፖሊሲ እና የህግ ማዕቀፍችን መዘርጋት እና አስቻይ ሁኔታዎች መፈጠራቸውን ማረጋገጥ ነው።

የዚህ እስትራተጂ ራዕይ እና ተልእኮ የሚሳካው የግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራትን አንቆ የያዘቸው ቁልፍ የእድገት ማነቆ መፈታትና ወደ ሚፈለገው እድገት አቅጣጫ መሸጋገር ሲችሉ ነው፡፡ በመሆኑም እስትራቴጂው ሰባት ቁልፍ ማነቆዎችና አንፃራዊ መፍትሔዎችን ለይቶ አስቀምጧል፡፡

## ቁልፍ ማነቆዎች

1. የኅብረት ሥራ ማኅበራት በአግባቡ ተግባሮቻቸውን በብቃት እየሰሩ መሆን አለመሆናቸውን፣ በተቆጣጣሪ እና በአገልግሎት ሰጪ አካላት የተሰጣቸውን ትኩረት እንዲሁም አርሶ አደሮች እና ከእሴት ሰንሰለት ተዋንያን ጋር ያላቸውን ግንኙነት መለካት የሚያስችል ግልፅ የሆኑ አመልካቾች አለመኖር፣ የችግሩ ማጠንጠኛ ኅብረት ሥራ ማህበራት አንዱ ከሌላው በተግባራቸው፣ በአመራር ብቃታቸው፣ ተልዕኳቸውን ማሳካታቸው የሚረጋገጥበት መለኪያ የለም፣ የብቃት ማረጋገጫ የሚሰጥ አካልም የለም፣ የዘረፉ ተዋናይ አሠራራቸውን የሚያውቁበት ሥርዓት አልተፈጠረም ነው፡፡ ስለሆነም የግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራት ውጤታማ እንዲሆኑ ይህ ቁልፍ ማነቆ መፈታት አለበት ነው፡፡

2.የኅብረት ሥራ ማኅበራት በአግባቡ ተግባሮቻቸውን ማከናወን የሚያስችሏቸው አቅም የሌላቸው መሆኑ እና የሚደረግላቸው የአቅም ግንባታ ድጋፍ አቅማቸውን በሚፈለገው መጠን ሊያጎለብት አለመቻሉ፣ ምክንያት የተለያየ የአቅም ግንባታዎች በተለያዩ አካላት በተበጣጠሰ መልኩ ይሰጣሉ፡፡ ይህም የአቅም ግንባታ ስራ በአንድ ማእከል ባለመሆኑ ክህሎትን እውቀትንና አመለካከትን ለማሻሻ አተኩሮ ሚሰጥ አልነበረም፡፡ በመሆኑም ይህ መሰረታዊ ማነቆ መፈታት አለበት፡፡

3.የግብርና ኅብረት ሥራ ማኅበራት የፋይናንስ አቅርቦት ስርዓት በዘላቂነት የኅብረት ሥራ ማኅበራት በአግባቡ ተግባሮቻቸውን ለማከናወን የሚያስፈልጓቸውን የፋይናንስ አገልግሎት ማግኘት አለመቻላቸው፣ የግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራት የግብይት ስራዎችን፣ የመሰረተ ልማት ግንባታዎችን፣ ሌሎች አስፈላጊ ጉዳዮችን ለመፈጸም እንዲችሉ ፋይናንስ ወሳኝ ቢሆንም የፋይናንስ ተቋማት ውስንነትና ሥርዓት አለመዘርጋት ምክንያት ተግባሮቻቸውን በአግባቡ መወጣት ስላልቻሉ ይህ ቁልፍ ማነቆ መፈታት ይኖርበታል፡፡

4.የኅብረት ሥራ ማኅበራት የሚሰሩበትን የግብይት መዋቅር እና መሰረተ ልማት በተለይም በምርት ግብይታቸው ለአባሎቻቸው ቀልጣፋና ውጤታማ አገልግሎት መስጠት የሚያስችል አለመሆኑ፣

5.በአግባቡ ተግባሮቻቸውን ለሚያከናውኑ ኅብረት ሥራ ማኅበራት የሚሰጡ ተጨማሪ አገልግሎቶች በሚፈለገው ደረጃ ላይ አለመድረስ፣

6.ለኅብረት ሥራ ዘርፍ የቁጥጥር እና የህግ ድጋፍ የሚሰጡ የመንግስት ተቋማት በመዋቅር፣ በአቅም እና በተጠሪነት ብቁ ሆነው በአግባቡ ተግባሩን የሚወጣ የኅብረት ሥራ ዘርፍ መፍጠርና መምራት አለመቻል፣

7.በአግባቡ ተግባሩን የሚያከናውን የኅብረት ሥራ ዘርፍን ለማልማት የሚያስችል የኅብረት ሥራ ፖሊሲ እና የህግ ማዕቀፍ በሚፈለገው ደረጃ አለመኖር፣

## የማነቆዎች መፍቻ ስትራቴጂያዊ ተግባራት

1.ቀጣይነትና ውጤታማ ተግባራትን ብቁ አመራር እና ጠንካራ አስተዳደራዊ መዋቅሮችን መሰረት ያደረጉ መስፈርቶችን በማዘጋጀት በአግባቡ ተግባሮቻቸውን የሚያከናውኑ ኅብረት ሥራ ማኅበራት ተለይተው የላቀ የብቃት ዕውቅና የሚያገኙበትን አሰራር ተግባራዊ ማድረግ፣

2.በትክክል በተቀረፀና በጊዜ በተገደበ የላቀ ብቃት ዕውቅና ለማግኘት በሚያስችል የአቅም ግንባታ አገልግሎት አሰጣጥን በማጠናከር እና በሂደት ይህ ተግባር በኅብረት ሥራ ኮሌጆች የልቀት ማዕከል እንዲከናወን ማድረግ፣

3.የግብርና ኅብረት ሥራ ማኅበራት የፋይናንስ አቅርቦት ስርዓት ዘላቂ ለማደረግ፡-

ሀ) የላቀ የብቃት እውቅና ላላቸው እና እውቅናውን ለማግኘት በሂደት ላይ ለሚገኙ የኅብረት ሥራ ማኅበራት ላይ ትኩረት የሚያደርግ ተዘዋዋሪ ፈንድ እና የብድር ዋስትና ስርዓት መዘርጋት፣

ለ) የማይክሮ ፋይናንስ ተቋማት/የገጠር ገንዘብ ቁጠባና ብድር ኅብረት ሥራ ማኅበራትን አቅም ማጠናከር እና የኢትዮጵያ ንግድ ባንክን ወይም የኢትዮጵያ ልማት ባንክ ለግብርና ኅብረት ሥራ ማኅበራት ማበደር እንዲችሉ አቅማቸውን ማስፋት፣

4.የኅብረት ሥራ ማኅበራትን የግብይት መዋቅር እና መሰረተ ልማት ማሻሻል፡-

ሀ) አርሶ አደሮች ከኅብረት ሥራ ማኅበራት ግብይት ቀጥተኛ ተጠቃሚ እንዲሆኑ የሚያስችል ቀልጣፋ የግብይት ሰንሰለት መዘርጋት እና የኅብረት ሥራ ዩኒዬኖች እና የመሰረታዊ ኅብረት ሥራ ማኅበራትን ምርት በኮሚሽን ላይ በተመሰረተ አሰራር ለገበያ እንዲያቀርቡ ማድረግ እና

ለ) የገበያ መረጃ ስርዓትን፣ የፍላጎት እና የአቅርቦት ግንኙነት ሰንሰለትን ማሻሻል፣

5.በአጭር ጊዜ ውስጥ ለኅብረት ሥራ ማኅበራት የሚሰጡ የኦዲት፣ የህግ እና የአደረጃጀት አገልግሎቶችን ማጠናከር እና በረጅም ጊዜ ውስጥ እነዚህ አገልግሎቶች በሂደት በኅብረት ሥራ እንቅስቃሴ እና ወይም በሌሎች የግል አግልግሎት ሰጪ ተቋማት እንዲሰጡ ማድረግ፣

6.የፌደራል እና የክልል የኅብረት ሥራ ማኅበራት ማስፋፊያ አካላትን መዋቅራቸውን፣ አቅማቸውን እና ተጠሪነታቸውን ማሻሻል፣

7.የተሟላ እና ወጥ የሆነ የኅብረት ሥራ ልማት ፖሊሲ እና የህግ ማዕቀፍ ማዘጋጀት ናቸው።

ይህ የግብርና ኅብረት ሥራ ዘርፍ ልማት ስትራቴጂ በግብርና ትራንስፎርሜሽን ካውንስል በ2004 ዓ/ም ጸድቆ በ2005 በጀት ዓመት መተግበር ጀምሯል። ስትራቴጅውን ለማስፈጸም ኃላፊነት የተሰጠው ለፌደራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ እና ለአራቱ የክልል ኅብረት ሥራ ማስፈፊያ ኤጀንሲዎች ነው። ስትራቴጂው ቅድሚያ መተግበር የጀመረው በትግራይ፣ በአማራ፣ በኦሮሚያ እና በደቡብ ብሄር በሄረሰቦችና ህዝቦች ክልሎች የግብርና እድገት ፕሮግራም ተግባራዊ በሚያደረጉ የተመረጡ ወረዳዎች ውስጥ ነው።

ስትራቴጂውን ለመተግበርም ሰነዱ በሶስት ዋና ማእቀፎችና በ13 የተለያዩ ክፍሎች ተከፍሎ ቀርቧል። በዝርዝሩ ሲቃኝ፣-

1.የኅብረት ሥራ ማህበራት ተግባራት

1. የምርት ግብዓት ግዥና ስርጭት
2. የኤክስቴንሽን አገልግሎት
3. የምርት ግብይት (ዕሴት መጨመርን በማካተት)
4. ትርፍ ክፍፍል
5. ሌሎች አገልግሎቶች (ምሳሌ ማስፋፋት፣ የፍጆታ እቃ ማቅረብ)

የኅብረት ሥራ የአደረጃጀት እርከን ደረጃ እና አስተዳደር

1. የኅብረት ሥራ የአደረጃጀት እርከን ደረጃ
2. የኅብረት ሥራ የውስጥ ሥራ አመራር እና አስተዳደር
3. የፌደራል እና የክልል መንግስታት ተግባርና ኃላፊነት (ኢንስፔክሽንን ጨምሮ)

3. ከባቢያዊ አስቻይ ሁኔታዎች

1. የፖሊሲ እና የህግ አስቻይ ከባቢያዊ ሁኔታዎች
2. የኅብረት ሥራ ፋይናንስ
3. የኅብረት ሥራ አቅም ግንባታ
4. የኅብረት ሥራ ኦዲትና የህግ አግልግሎት
5. የኅብረት ሥራ ማኅበራትን ማደራጀት ናቸው።

እነዚህን መሰረታዊ ጉዳዮች ጠንቅቆ አውቆ መተግበር የሚቻለው ስትራቴጂውን ሁሉም የኅብረት ሥራ አካላት ተረድተውት ወደ ራሳቸው ለውጠው መተግበር ሲችሉ ነው። በዋናነት የጉዳዩ ባለቤት የሆኑት ኅብረት ሥራ ማህበራት ይህንን ስትራቴጂ ተግባራዊ ለማድረግ ቁርጠኝነትን ይጠይቃቸዋል።

የተለምዶ አሰራራቸውን ቀይረው በዚህ ስትራቴጂ በተቀመጠው አግባብ መሰረት መመራት የግድ ይላቸዋል። ከኅብረት ሥራ ማስፋፊያ አካላት ለግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራት የሚደረግላቸው ቴክኒካል እገዛና ሌሎች ህጋዊ ድጋፎች ይህንን ስትራቴጂ አስመልክቶ መሆን አለበት።

በዚህ ኃላፊነት መጠን ይህ ለሀገራችን ኅብረት ሥራ ህዳሴ መሠረት እንደሚጥል ተስፋ የተጣለበት እስትራቴጂ ተግባራዊ በማድረግ ሰባቱን ማነቆዎች ለመፍታት ከጅምሩ ምን መሠረታዊ ተግባራት መፈፀም ተጀምሯል? በማለት ለጠየቅነው የሚከተለው ምላሽ ተገኝቷል።

የስትራተጂው የበላይ አስኳል በጠቅላይ ምኒስትሩ የሚመራ የግብርና ትራንስፎርሜሽን ካውንስል ተቋቁሟል። በተዋረድ በግብርና ሚኒስቴር የበላይ መሪነት የክልል የግብርና ቢሮ ሀላፊዎች ያሉበት አስተባባሪ ኮሚቴ ተውቅሯል። በተመሳሳይ ሁኔታ በክልል ደረጃ ስትራቴጂው ተግባራዊ የሚሆንባቸው ዞኖች ያሉ አስተዳዳሪዎችና የግብርና የኅብረት ሥራ ማስፋፊያ አካላት ያቀፈ የክልል አስተባባሪ ኮሚቴዎች በአራቱም ክልሎች ተቋቁሟል። እንደፈፃሚ ተቋም በፌደራል እና በክልል ኅብረት ሥራ ማስፋፊያ ኤጀንሲዎች ስትራቴጂ ትግበራውን የሚከታተሉ የግብርና ኅብረት ሥራ ዘርፍ ልማት ስትራቴጂ ሴክሬተሪያት ተዋቅሯል። ሴክሬተሪያቱ የእስትራቴጂውን ሠነድ ከእንግሊዝኛ ወደ አማርኛ ቋንቋ በመመለስ ታትሞ እንዲሰራጭ አድርጓል። እንዲሁም እስትራቴጂው የሚፈፀምባቸው ክልሎችና ኅብረት ሥራ ማህበራት ያሉበት ደረጃ ለመለየት ሁሉን ያሳተፈ ግምገማ ተደርጓል። በግምገማው ውጤት በ2005 በጀት ዓመት ትኩረት ተሰጥቶ እንዲሰራበት ስምምነት የተደረሰበት በሰሊጥ ግብይት ለተሰማሩ ኅብረት ሥራ ዩኒየኖች ቅድሚያ ድጋፍ ማድረግ በቀጣይ የቡና ግብይት ኅብረት ሥራ ማህበራትን መደገፍና ተጓዳኝ ሥራዎችን መፈፀም ነው። በዚሁ መሠረት በእስትራተጂው ትግበራ የመጀመሪያ ዓመት የተመዘገቡ ውጤቶች፣-

## 1. የኅብረት ሥራ የላቀ ብቃት ዕውቅና ለመስጠት

ቅድመ ዝግጅት ሥራ በኅብረት ሥራ ማህበራት የላቀ ብቃት ማረጋጫ አሰጣጥ ጥናት እንዲደረግ በግብርና ትራንስፎርሜሽን ኤጀንሲ አማካኝነት ለእንግሊዝ ኅብረት ሥራ ኮሌጅ ተሰጥቶ ለአንድ አመት ጥናቱ ሲጠና ቆይቶ አሁን ለትግበራ በሚያመች መልኩ እየተዘጋጀ ይገኛል። በቀጣይ አመት በተወሰኑ ኅብረት ሥራ ማህበራት ላይ ተግባራዊ ይሆናል ተብሎ ይጠበቃል።

## 2. የኅብረት ሥራ የልዕቀት ማዕከል ማቋቋም በተመለከተ፣

አርዳይታ ኅብረት ሥራ ኮሌጅ የልዕቀት ማዕከል ሆኖ እንዲያገለግል ተመርጧል። በግብርና ትራንስፎርሜሽን ኤጀንሲ አማካኝነት በእንግሊዝ ኅብረት ሥራ ኮሌጅ ውስጣዊ አደረጃጀቱና ለልዕቀት ማዕከል ብቃቱን ማጥናት፣ የውስጥ አሰራር ችግሮች መለየት፣ የስልጠና ስርዓት ትምህርት ማዘጋጀት እና ኮሌጁን ወደ ልዕቀት ማዕከልነት የሚያሸጋግር ቢዝነስ ፕላን ዝግጅት እየተሠራ ነው።

## 3. የኅብረት ሥራ የፋይናንስ አቅርቦትን ማሻሻል

በስትራቴጂው ትግበራ ጅምር ዓመት ለ9 ኅብረት ሥራ ዩኒየኖች የፋይናንስ አቅርቦት እንዲመቻችላቸው ድጋፍ ተደርጓል። በተሰጠው ድጋፍ ዩኒየኖች ከአባሎቻቸው ምርት በማሰባሰብ ግብይት እንዲፈፅሙ ብር 354,614,444 ብድር ማግኘት ችለዋል።

| ተ.ቁ | ክልል | ብድር ያገኙ ዩ/ሥ/ ዩ ብዛት | የተሰማሩበት ሰብል | የተገኘ ብድር መጠን |
|---|---|---|---|---|
| 1 | ትግራይ | 1 | ሰሊጥ | 25,000,000 |
| 2 | አማራ | 4 | ሰሊጥ | 100,000,000 |
| 3 | ደቡብ ብ/ብ/ህ/ | 2 | ቡና | 207,614,444 |
| 4 | ኦሮሚያ | 2 | ቡና | 22,000,000 |
| ድምር | | 9 | | 354,614,444 |

## 4. የኅብረት ሥራ ማኅበራትን የግብይት መዋቅር እና መሰረተ ልማት ማሻሻል

የግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራት ግብይት ሰንሰለት ለማሳጠር ትኩረት ተደርጎ እየተሠራ ነው። በሰሊጥ፣ በቡና፣ በስንዴ፣ በጤፍ፣ በገብስ፣ በሽንብራ ግብይት የተሰማሩ ኅብረት ሥራ ዩኒየኖች አመራር አካላት እና ለኅብረት ሥራ ማስፋፊያ አካላት ወደ ግብይት ሊያስገባ የሚችል ስልጠና ተዘጋጅቶ ተሰጥቷል።

ለግብይት ቅድመ ዝግጅት ድጋፍ አሰጣጥ ምቹ እንዲሆን 43 የኅብረት ሥራ ዩኒየኖች ተመርጠዋል። ቅድሚያ በሰሊጥ በመቀጠል በቡና ግብይት ለተሰማሩ ኅብረት ስራ ዩኒየኖች እና በሌሎች የግብርና ምርቶች የትኩረት ቅደም ተከተል ተቀምጧል። በዚሁ መሠረት የስትራቴጂው ትግበራ የመጀመሪያ ዓመት በተደረገ የጋራ ጥረት 4 ዩንየኖች 18,350 ኩንታል ሰሊጥ ለውጭ ገበያ እንዲልኩ በተደረገው ድጋፍ 3,054,580 የአሜሪካ ዶላር ገቢ ለማግኘት ተችሏል።




በዚህ የግብይት ድጋፍ የኮሚሽን አሰራር በኅብረት ሥራ ማህበራትና ዩኒየኖች መካከል እንዲጀመር መሰረት ተጥሏል፡፡ በዚህም የኅብረት ሥራ ማህበራቱ የመደራደር አቅም እንዲጎለብት ሆኗል፡፡

### በ2005 ዓ.ም ግብይት ያከናወኑ ዩንየኖች

| [illegible] | እቅድ | [illegible] | [illegible] | | [illegible] | [illegible] |
|---|---|---|---|---|---|---|
| | | | [illegible] | [illegible] | | |
| ሰቲት | 70000 | 7114 | | 5700 | 1414 | 874000 |
| መተማ | 230628 | 13115 | 7985 | 3990 | 1140 | 694260 |
| [illegible] | 142000 | 8089 | 1709 | 6380 | | 1110120 |
| [illegible] | - | 3704 | | 2280 | 1424 | 376200 |
| ጠቅላላ ድምር | 442628 | 32021.7 | 9694 | 18350 | 3977.66 | 3054580 |

ምንጭ ሪጉላቶሪ ዳሬክቶሬት

በዚህም እንቅስቃሴ በፌደራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ ተቋርጦ የነበረው የውጭ ግብይት ድጋፍ በስተራተጂው እንዲጀምር ተደረጓል፡፡

በዚህኛው አሠራር ከዚህ በፊት ማህበራቱ ምርቶቻቸውን ለውጭ ገበያ ለመላክ ይጠቀሙበት የነበረውን ረጅም አካሄድ በማሻሻል በህጋዊ ሰውነት ማረጋገጫ ብቻ መላክ እንዲችሉ ከብሄራዊ ባንክ ጋር ስምምነት ላይ ተደርሶ እንዲስተናገዱ ተደርጓል፡፡

## 5. የግብይት መሰረተ ልማት ማሻሻል

የግብይት መሰረተ ልማት ግንባታ የስትራቴጂው አንዱ አካል ነው፡፡ ተግባሩን ለመፈፀም ጅምር ሰራዎች እየተከናወኑ ነው፡፡ በመጀመሪያ የግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራት አቅም ገንቢዎችን በመለየት እና ለኅብረት ሥራ ማህበራቱ የሚሰጡት ድጋፍ በስትራቴጂው መሰረት እንዲሆን ከአቅም ገንቢዎች ጋር በመወያየት የጋራ መግባባት እንዲፈጠር ተደርጓል፡፡ በዚህ መሰረት ከአግሪቴራ እና ከኤስ ኤን ቪ ጋር የመግባቢያ ሰነድ ተፈረሟል፡፡

ከUSAID በተገኘው ድጋፍ በሁለት ክልሎች ለአራት የሰሊጥ ግብይት ዩኒየኖች 5000 ሜ/ቶን የሚይዙ አራት መጋዘኖች መገንባት ተጀምሯል፡፡ እያንዳንዱ መጋዘን 5000 ቶን መያዝ አቅም አለው፡፡ የወጪው ግምት ብር 37,615,926.00 እንደሚሆን ተገምቷል፡፡ የዚህ ወጪ ብር 26,240,066.60 በዩኤስ አይዲ ግራንት ቀሪው ብር 11,375,859.40 በዩኒየኖች እንደሚሸፈን ታቅዷል፡፡

| ተ.ቁ | ግንባታ የጀመረው ዩንየን | የወጪ ድርሻ በብር | | |
|---|---|---|---|---|
| | | ዩ ኤስ አይዲ 70 ከመቶ | ዩንየን 30 ከመቶ | ጠቅላላ ወጪ |
| 1 | ሰላም ዩኒየን | 6,601,126.00 | 2,959,170.00 | 9,560,296.00 |
| 2 | መተማ ዩኒየን | 6,507,774.95 | 2,789,047.00 | 9,296,821.95 |
| 3 | ዳንሻ ዩኒየን | 6,268,814.35 | 2,686,634.70 | 8,955,449.05 |
| 4 | ሰቲት ዩኒየን | 6,862,351.30 | 2,941,007.70 | 9,803,359.00 |
| | ድምር | 26,240,066.60 | 11,375,859.40 | 37,615,926.00 |

ምንጭ ሪጉላቶሪ ዳሬክቶሬት



6. የኅብረት ሥራ ኦዲት እና የህግ አገልግሎትን ማሻሻል

የኅብረት ሥራ ኦዲት ጥራትና ተደራሽነትን እና የህግ አገልግሎት ጥራትና ተደራሽነት ለማሻሻል እንዲቻል በፌደራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ አማካኝት አንድ አገራዊ የሆነ የኅብረት ሥራ ኦዲት ማንዋል እንዲዘጋጅ ተደርጓል፡፡ በመመሪያው ላይ ዕቡል ግንዛቤ እንዲፈጠር ከክልል እስከ ወረዳ ለሚገኙ የኅብረት ሥራ ኦዲተሮች ስልጠና ተሰጥቷል፡፡ በተፈጠረው አቅም ጅምር ስራዎች እየተከናወኑ ይገኛል፡፡

7. የፌደራል እና የክልል የኅብረት ሥራ ማኅበራት ማስፋፊያ አካላትን መዋቅራቸን፣ አቅማቸውን እና ተጠሪነታቸውን ማሻሻል፣

የፌደራልና የክልል የኅብረት ሥራ ማስፋፊያ አካላት ለተለያዩ ተቋማት ተጠሪ መሆን በአገልግሎት አሰጣጥ ስትራቴጂውን ወጥ በሆነ መልኩ ለመምራት ይቸግራል፡፡ ይህንን የተጠሪነት ችግር እንዲፈታ በግብርና ትራንስፎርሜሽን ካውንስል ተወስኗል፡፡ በመሠረት በፌደራል ደረጃ ለግብርና በወሳኔው ሚኒስቴር፣ በክልል ደረጃ ከደቡብ ብሄር ብሄረሰቦች እና ህዝቦች ክልል በስተቀር ሌሎች ተጠሪነታቸው ለግብርና ቢሮ እንዲሆኑ ተደርጓል፡፡ የደቡብ ክልል የኅብረት ሥራ ማስፊፊያ አካሉ በቢሮ ደረጃ የተዋቀረ በመሆኑ እንዳለ እንዲቀጥል ሆኗል፡፡

8. ግንኙነትን ማጠናከርና ክትትል ሥራ

የኅብረት ሥራ ዩኒየን አመራሮች እና ስራ አስኪያጆች እንዲሁም ከትግራይና ከአማራ ክልል የተውጣጡ የህብረት ሥራ ማስፋፊያ አካላትና የግብርና ባለሙያዎች 31 ከምርት ገበያ 1፣ ACID/VOCA 3፣ ከኢትዮጵያ ግብርና ትራንስፎርሜሽን ኤጀንሲ 5፣ ከአግሪቴራ 1፣ ከኤስ ኤን ቪ 2 በአጠቃላይ 85 ተሳታፊዎች የ2005ዓ.ም አፈጻጸም በጋራ ገምግሟል፡፡ ተያይዞም በ2006 ዓ/ም ለሚከናወኑ ተግባራት፣ የዩኒየኖችና ፈጻሚ አካላት ከአቅም ገንቢዎች ጋር ስለሚኖራቸው ትስስር የጋራ ግንዛቤ ተይዟል፡፡

ሆኖም ከአቅም ገንቢዎች የተወሰኑት ACID/VOCA - አግሪቴራ -ክኖስርብ - ሳሳካዋ ግሎባል 2000 ፋርም አፍሪካ - የአለም ምግብ ፕሮግራም ኤስ ኤን ቪ እና ኑፊክ ተግባሮቻቸውን በስትራቴጂው መሰረት መፈፀም ደረጃ ላይ አለመሆናቸው ታውቋል፡፡ በዚህ አጋጣሚ የተገባው ቃል-ኪዳን እንዲፈፀም ግንኙነቱ መጠናከር እንደሚገባው መጠቆም እንወዳለን፡፡

በአጠቃላይ ራዕዩ እንዲሳካ በቀጣይ ስትራቴጂውን አጠናክሮ በመቀጠል በተለይ ያልተጀመሩ ተግባራትን በማካተት፣ በጅምር ላይ ያሉ ስራዎችንን በማጠናከር ስትራቴጂው ላይ እንደተቀመጠው ተግባሮቻቸውን በአግባቡ የሚወጡ የግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራትን በመፍጠር እና የዚህን ተሞክሮ በሁሉም አገሪቱ ክፍል ማስፋት ይገባል እንላለን፡፡

# አበይት ክንውኖች

ከኢትየጵያ ድህነትንና ኋላቀርነትን ለማስወገድ መንግስት የነደፋቸውን የልማት ፖሊሲዎች ስትራቴጂዎችና ዕቅዶች እውን ለማድረግ ከምንጊዜውም የበለጠ የሁሉንም ጥረት የሚጠይቅበት ደረጃ ላይ መገኘታችን እሙን ነው፡፡ በተለይም የኅብረት ሥራ ማኅበራት ሕዝብን ተጠቃሚ የሚያደርግ የልማት ፖሊሲ ለመተግበር ሶስተኛ የልማት አማራጭ በመሆናቸው ብዙ ድርሻ ይጠበቅባቸዋል፡፡

በኢኮኖሚው ውስጥ መሪ የሆነው የግብርናው ዘርፍ በከፍተኛ ፍጥነት አድጎ ወደ ኢንዱስትሪው እንዲሸጋገር የአርሶ አደሩን የአመራረት ዘይቤ መለወጥ፣ አዳዲስ ቴክኖሎጂዎችን አሰራሮችንና የምርት ግብዓቶችን በጊዜና በቦታ ማሟላት ይጠይቃል፡፡ ለዕቅዶቻችን ማስፈፀሚያ የሚጠይቀንን መዋእለ ንዋይና የሀገር ውስጥ የፋይናንስ እጥረትን ለመቀነስ የቁጠባ ባህላችንን ማሳደግ ወቅታዊ ጉዳይ ነው፡፡ በመሆኑም የአግሮ ፕሮሰስ ኢንዱስትሪዎችን በገጠር ማዳረስና የገበያውን ሥርዓት ማሻሻል ደግሞ የማይታለፍ ተግባር ነው፡፡

የኅብረት ሥራ ማኅበራትም ይህንን ሁሉ ኃላፊነት በንቃት ለመወጣት እየሠሩ ነው፡፡ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ልማት በማስፋፋት የሕዝቡን የልማትና ፍትሀዊ ተጠቃሚነት ለማረጋገጥ የማይተካ ተግባርም እየፈፀሙ ነው፡፡

የፌደራልና የክልል ኅብረት ሥራ ኃላፊዎችና ባለሞያዎች የ2005 ዓ.ም 9ወራት አፈፃጸም በጋራ ሲገመገም



ቅንብር በአበራ በቀለ

ጤናማ የኅብረት ሥራ ማኅበርና ተቋማት ለመፍጠር ሥራዎቻቸውንም እንዲያቀላጥፉ የቴክኒክ ድጋፍ ለመስጠትና በሕጎቻቸው መሠረት መሥራታቸውንም ለመቆጣጠር መንግሥት በፌዶራልና በክልል ደረጃ መዋቅር ዘርግቷል፡፡ በአምስት ዓመቱ የዕድገትና ትራንስፎርሜሽን ዕቅድ በኅብረት ሥራ ዘርፍ የኅብረት ሥራ ማህበራትን አደረጃጀት፣ አሠራርንና የሰው ሀይል አቅምን በማሻሻል የኅብረት ሥራ ማህበራት ለማስፋፋት የሚያስችሉ ተግባራት ታቅደዋል፡፡

በተዘረጋው የአሠራር ሥርዓትም በ2005 ዓ.ም የበጀት ዘመን 9 ወራት የተፈፀሙ የኅብረት ሥራ ዘርፍ አበይት ክንውኖች በሚከተለው መልኩ ተቃኝተዋል፡፡

## የኅብረት ሥራ ዘርፍ ሪፎርም አተገባበር

የዓለምና የሀገራችን ተጨባጭ ሁኔታ ሥራዎቻችንና የምንሰጣቸውን አገልግሎቶች ፈጣን እንዲሆኑ ይጠይቃል፡፡ የፌደራል ኅብረት ሥራ ኤጀንሲ የተሰጠውን ተልዕኮ ተግባራዊ ለማድረግ በዚሁ የተለካ ቁመና ሊኖረው ይገባል፡፡ ቀልጣፋ የሆነ አሰራር ማስፈን የሚችል ቁመና እንዲፈጠር ተቋማዊ አደረጃጀት ወሳኝ በመሆኑ በመሠረታዊ የሥራ ሂደት ጥናት አሠራሩን ፈትሾ ቀድሞ የነበረውን የሥራ ሂደት በማሻሻል በሁለት የቴክኒክ የሥራ ሂደቶች እና ምንም የአሰራር ሥርዓት ያልተጠናላቸው የድጋፍ ሰጪ የሥራ ሂደቶችን ጥናታቸው እንዲጠናቀቅ በማድረግ አምስት የሥራ ሂደቶችን በማደራጀት ወደ ሥራ እንዲገቡ ተደርጓል፡፡ በዚህም ለውጥ ምክንያት የህዳሴውን እቅዶቻችንን ለማሳካት ሁሉም የድርሻውን የሚያበረክትበት ምቹ የሥራ ሁኔታ ለመፍጠር ጥረት እየተደረገ ነው፡፡

ሁሉን አቀፍ የሴቶችን ተጠቃሚነት ለማረጋገጥ ዕቅድ ሲዘጋጅ፣ ፕሮግራሞች ሲቀረፁና ሲተገበሩ እንዲሁም በሌሎች ጉዳዮች ላይ ሴቶችን የሚመለከቱ መሠረታዊ ጉዳዮች በአግባቡ እንዲካተቱ የሚከታተል ባለሞያ በቀድሞ አደረጃጀት ስላልነበረ በቅጥር እንዲሟላ ተደርጓል፡፡

በዚሁ መሠረት ሠራተኛው የሀገራችንን ህዳሴ ጉዞ መሠረታዊ ጉዳዮች ጠንቅቆ አውቆ በመረዳት የበኩሉን ሚና እንዲጫወት ለማድረግ እና የሲቪል ሰርቪስ የለውጥ ሠራዊት ግንባታ አተገባበር የተሟላ ግልፅኝነትን ለመፍጠር እና ለዜጎች ቀልጣፋ፣ ተጠያቂነትና ጥራት ያለው፣ ፍትሃዊና እኩልነትን ያረጋገጠ መንግስታዊ አገልግሎት ለማቅረብ እንዲቻል በዜጎች ቻርተር ላይ አቅሙ እንዲገነባ ተደርጓል፡፡

በፕሮግራም በጀት አሠራር መሠረት ዕቅድ በማዘጋጀት ሠራተኞች ሥራዎችን በውጤት ተኮር የአሠራር ሥርዓት መሠረት ተፈራርመው ማከናወን ጀምረዋል፡፡ በየደረጃው የሚገኙ ፈፃሚዎች ሥራዎችን በጋራ ይገመግማሉ፡፡ ስለሆነም ለስኬቱ ጅምሩ ተጠናክሮ እንደሚቀጥል ተስፋው ብሩህ ነው፡፡

## የኅብረት ሥራ ንቅናቄ መድረክ

ኅብረት ሥራ ማኅበራት ደህንነታቸው ተጠብቆ የተቋቋሙበትን ዓላማ እንዲያሳኩ ያሉበትን ተጨባጭ ሁኔታ የሚያሳውቅ የዘርፉ ተዋንያን በጋራ የሚመክሩበት ነው፡፡ በመሆኑም ሁሉም ድርሻውን አውቆ ለመፍትሔ እንዲተጋ የሚነቃቃበት ነው፡፡ ይህንንም ዓላማ ለማሳከት በአማራ እና በትግራይ የተካሄዱትን ያለፈዉን ዓመት መድረኮች ጠንካራና ደካማ ጎኖች በመገምገም በድጋሚ መድረኩን ማካሄድ አስፈላጊ ሆኖ በመገኘቱ የተዘጋጀዉን የንቅናቄ ሰነድ እንደገና በመከለስና በማዘጋጀት መድረኩ እንዲካሄድ ለማድረግ የሚያስችል የቅድመ ዝግጅት ስራዎች ተሰርተው ከክልል ጀምሮ እስከ መሠረታዊ ኅብረት ሥራ ማኅበራት ድረስ በተጠናከረ ሁኔታ በመካሄድ ላይ ይገኛል፡፡

በደቡብ ብ/ብ/ሕ ክልል በ2004 ዓ.ም በተጠናከረ ሁኔታ ንቅናቄው የተካሄደ ሲሆን በ2005 ዓ/ም ንቅናቄ ያልተካሄደባቸውን ቀበሌዎች በመለየት ንቅናቄውን አስቀጥሎ እየተሄደበት ነው፡፡ በኦሮሚያ ክልል በ2004 ዓ.ም ቅድመ ዝግጅት ሥራዎች ተጠናቀው በዚህ ዓመት ሥር ነቀል ንቅናቄ በመካሄድ ላይ ይገኛል፡፡

በአዲስ አበባ አስተዳደር፣ ድሬዳዋ አስተዳደርና ቤንሻንጉል ጉምዝ ክልሎች የንቅናቄ ሰነድ በማዘጋጀት ጅምር ሥራዎች ላይ መሆናቸውን ከሪፖርቶች መረዳት ተችሏል፡፡ ሱማሌ፣ አፋርና ጋምቤላ የንቅናቄ ሰነድ አዘጋጅተው የበጀት ሁኔታዎችን በመጠባበቅ ላይ በመሆናቸው በቀጣይ ንቅናቄው የተሟላና ሀገራዊ እንዲሆን ትኩረት ይጠይቃል፡፡

እስካሁን በተደረገው የተቀናጀና የተደራጀ ጥረት የኅብረት ሥራ ንቅናቄ በተሳካባቸው አካባቢዎች የሚከተለውን ውጤት ተመዘግቧል፡፡

የአመለካከትና የአስተሳሰብ ለውጥ እንዲመጣና፣ የአባላት የባለቤትነት ስሜት እንዲጎለብት ተደርጓል፣ የአመራር ትኩረት ተሻሽሏል፣ የገንዘብ ጎድለትና ብክነት እንዲሁም የብድር አመላለስ ሁኔታ ተሻሽሏል፣ የማህበራትን ገንዘብና ንብረት የሚመዘብሩ አመራሮች ከኃላፊነታቸው እንዲነሱና ለሕግ እንዲቀርቡ ከፍተኛ አስተዋፅዖ ከመደረጉም በላይ የአባላት ቁጥር እንዲጨምር ከፍተኛ እገዛ ማድረጉም በየአካባቢው ተመዝግቧል፡፡



የሁለገብ ገበሬዎች ኅብረት ስራ ማህበራት የንቅናቄ መድረክ /አማራ ክልል/

## የኅብረት ሥራን ማደራጀት

ዜጎችን ከድህነት የሚያላቅቁ ሀገርን ወደ ዕድገት የሚያሸጋግሩ የኅብረት ሥራዎችን ማስፋፋት የዘርፉ ዋና ተግባር ነው:: በመሆኑም የኅብረት ሥራ ልማትን ዘላቂ የዕድገት ምንጭ አድርጎ ለማስቀጠል በየደረጃው በሚገኙ በኀብረት ሥራ ማህበራት ማስፋፊያ አካላት በበጀት ዓመቱ 9 ወራት ውስጥ ሠፊ ሥራ ተሰርቷል::

የአባላትን ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ችግሮች ሊያቃልሉና ለዕድገትና ትራንስፎርሜሽን ዕቅድ መሳካት የበኩላቸውን አስተዋፅኦ ሊያበረክቱ የሚችሉ 1,078,112 ወንድ 604,070 ሴት በድምሩ 1,682,182 አባላት እና 325,739,663 ብር ካፒታል ያላቸው 3,991 መሠረታዊ የኅብረት ሥራ ማኅበራትና 45 የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች ለማደራጀት ታቅዶ 563,439 ወንድ 195,467 ሴት በድምሩ 758,906 አባላት እና 122,245,042 ብር ካፒታል ያላቸው 4,808 የተለያዩ መሠረታዊ የህብረት ስራ ማህበራት ተደራጅተዋል:: ከዚህ በተጨማሪ በመሠረታዊ የኅብረት ሥራ ማኅበራት ደረጃ ያሉ የአቅም ችግሮችን ሊፈቱና አባላትን ይበልጥ ተጠቃሚ ሊያደርጉ የሚችሉ 28 የኅብረት ሥራ ዩኒየኖች ተደራጅተዋል::

## የአሠራር ሥርዓት ዝርጋታ

ከተለምዷዊ አሰራሮች ተላቆ በተሻሻሉ አሠራሮች ውጤት ለማምጣት አዲስ ሥርዓት መትከል ይጠይቃል:: ሥርዓቱን ፀንቶ የሚያቆመው ደግሞ ሕግና መመሪያ መሆኑ አይካድም:: ስለዚህ በኅብረት ሥራ ዘርፍ ሥርዓቱን ለማስረፅ ሁልጊዜም ችግሮችን በመለየት የመመሪያ ዝግጅት በዕቅድ ተይዞ ይሠራል:: እስካሁን ከ 17 በላይ መመሪያዎች ፀድቀው በስራላይ ውለዋል:: ዘንድሮም የህብረት ስራ ማህበራት ያለባቸውን የፋይናንስ ስርዓት ችግር ለመቅረፍ ወጥ የሆነ የፋይናንስ አጠቃቀም መመሪያ ተዘጋጅቶ ቀርቧል::

ቀደም ሲል በኤጀንሲው የተዘጋጁትን የኅብረት ስራ የሰው ሃይል አስተዳደር፣ ግብይት መመሪያ እና የግገር መመሪያዎች ያሉባቸውን ክፍተቶች በመለየት የማሻሻያ ፍሬም ወርክ ተዘጋጅቷል:: በተጨማሪም 2 ሞዴል የንግድ ሥራ እቅድ (Business Plan) የመጀመሪያው ረቂቅ ሠነድ ተዘጋጅቶ ለአስተያየት ቀርቧል::

## የኅብረት ሥራ ጥናትና ምርምር

በማያቋርጥ የልማት እንቅስቃሴ ውስጥ የሚያልፍ የልማት ተቋም የተሻለ ደረጃ እንዲደርስ በምርምር የታገዘ መሆን እንዳለበት ይታመናል:: በዚህ እምነት የኅብረት ሥራ ዘርፍ ማነቆዎችን ለመለየት ጥንካሬዎችንና ተሞክሮዎችን ከአንዱ ክልል ወደሌላው ለማድረስ የጥናትና ምርምር ሥራዎች በመደበኛነት ይሠራሉ:: በዚህ መስክ ባለፉት ዘጠኝ ወራት

- በማዕድን የኅብረት ሥራ ማኅበራት ችግሮችና መፍትሔዎቻቸው፣
- በመሠረታዊ እና በዩኒየኖች የኅብረት ሥራ ማኅበራት መካከል በሚደረጉ ግንኙነቶች ላይ የሚታዩ ችግሮችና መፍትሔዎቻቸው እና
- የኅብረት ሥራ ማስፋፊያ አካላት የአገልግሎት አሰጣጥ ሠነድ ዝግጅት ጥናቶች በመካሄድ ላይ ናቸው::

## የኅብረት ሥራ ትምህርትና ስልጠና

በኅብረት ሥራ ዘርፍ የሚታየውን የመፈፀምና የማስፈፀም አቅም ክፍተት ለማጥበብ የኅብረት ሥራ ንድፈ ሀሳብና ትግበራ፣ የኅብረት ሥራ አደረጃጀት፣ ሥራ አመራርና የኅብረት ሥራ ግብይት እንዲሁም የንግድ ዕቅድ አዘገጃጀት ላይ የስልጠና ማንዋሎች ተዘጋጅተዋል በተጨማሪም በፕሮጀክትና በመደበኛ ፕሮግራም የተለያዩ ስልጠናዎችን ተሰጥተዋል::

ባለፉት ዘጠኝ ወራት በኅብረት ሥራ ዘርፍ ለ88,135 የህብረት ስራ ማህበራት አመራር አካላት፣ ለ27,226 የህብረት ስራ ማህበራት ቅጥር ሠራተኞችና ለ2,391,010 የህብረት ስራ ማህበራት አባላትና ለ3,812 የህብረት ስራ ባለሙያዎች ትምህርትና ስልጠና ለመስጠት ታቅዶ ለ 51,498 የህብረት ስራ ማህበራት አመራር አካላት፣ ለ4,130 የህብረት ስራ ማህበራት ቅጥር ሠራተኞችና ለ2,650,460 የህብረት ስራ ማህበራት አባላትና ለ1,682 የህብረት ስራ ባለሙያዎች ስልጠናዎች በፌደራልና በክልሎች ተሰጥተዋል::

## የኅብረት ሥራ ኢንስፔክሽን

የህብረት ስራ ማህበራትን ደህንነት በመመርመር ችግሮችን የሚያሣይ መሣሪያና ሥርዓት አንዱ የኅብረት ሥራ ኢንስፔክሽን ስራ ነው፡፡ ከሕጎች፣ ከደንቦችና መመሪያዎች ያፈነገጡ አሰራሮችን ፈጥኖ የሚያቃና የማስጠንቀቂያ ደወልም ነው፡፡ በዘርፉ ተግባሩን እንደወትሮው ለመወጣት በዚህ ዓመት ለ21,392 መሠረታዊ የኅብረት ሥራ ማኅበራትና ለ209 የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች የኢንስፔክሽን አገልግሎት ለመስጠት ታቅዶ በ15,079 መሠረታዊ የህብረት ስራ ማህበራትና በ205 የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች የኢንስፔክሽን ሥራ ተካሂዷል፡፡ ኢንስፔክሽን በተካሄደባቸው በአንዳንድ ኅብረት ሥራ ማኅበራት ላይ የኅብረት ሥራ ማኅበራት ሕጎችን አክብሮ አለመንቀሳቀስ የተስተዋለ ሲሆን ይህንንም ለማስተካከል የተለያዩ እርምጃዎች በመወሰድ ላይ ናቸው፡፡

## የኅብረት ሥራ ኦዲት አገልግሎት

በኅብረት ሥራ ማኅበራት ጤናማ የፋይናንስ እንቅስቃሴ እንዲኖር በዓመት አንድ ጊዜ የኦዲት አገልግሎት ለሁሉም ማህበራት ማዳረስ በሕግ የተደነገገ ግዴታ ነው፡፡ ሕጉን ለመፈፀምም ባለፉት 9 ወራት ለ18,762 መሠረታዊ የኅብረት ሥራ ማኅበራትና ለ185 የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች የኦዲት አገልግሎት ለመስጠት ታቅዶ ለ8,107 መሠረታዊ የኅብረት ሥራ ማኅበራትና ለ92 የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች የኦዲት አገልግሎት ተሰጥቷል፡፡

በኦዲት አገልግሎቱ የኅብረት ሥራ ማኅበራት ያገኙት የትርፍና የኪሳራ መጠን እንዲሁም የጉድለት መጠን ተለይቷል፡፡ በሂሣብ ምርመራው ብር 21,510,842.46 ጉድለት ሲመዘገብ 168,556,539 ብር ደግሞ የተጣራ ትርፍ መሆኑ ተረጋግጧል፡፡ ከተገኘው የተጣራ ትርፍ 88,258,079 ብር ለአባላት የትርፍ ክፍፍል ተካሂዶ ቀሪው ደግሞ የማህበራቱን ጠቅላላ ጉባኤ ውሳኔ የሚጠብቅ ሆኗል፡፡

## የኅብረት ሥራ ህግ ጉዳዮች

የኅብረት ሥራ ማህበራት ሀብትና ንብረት በሕገወጦች የምዝበራ መረብ ተጨልፎና ባክኖ ልማቱ እንዳይቀጭጭ በዘርፉ የሕግ ድጋፍ ይደረጋል፡፡ በዚሁ መሠረት የኅብረት ሥራ ማኅበራትን ወክሎ ክስ ለመመስረት እንዲሁም የምክር አገልግሎትና ሌሎች የህግ ድጋፎችን ለመስጠት ለ 5,412 መሠረታዊ የኅብረት ሥራ ማኅበራትና ለ72 የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች የሕግ አገልግሎት ለመስጠት ታቅዶ ለ2599 መሠረታዊ የህብረት ስራ ማህበራትና ለ42 የህብረት ስራ ዩኒየኖች የሕግ ድጋፍ አገልግሎት ተሰጥቷል፡፡ በተሰጠው ድጋፍም በልዩልዩ ምክንያት የባከነ ገንዘብ ተሰብስቧል፡፡ በኢንቨስትመንት ሕጉ የተፈቀደው ጥቅምም እንዲከበር ተደርጓል፡፡

## የግብአት አቅርቦት

የአርሶ አደሩንና የአርብቶ አደሩን ምርትና ምርታማነት በማሳደግ በኩል ከፍተኛ አስተዋፅዖ ያላቸውን የተሻሻሉ ግብዓቶችን በተመጣጣኝ ዋጋና በወቅቱ ባሉበት ቦታ ለማድረስ 4,829,140 ኩ/ል ዳፕ፣ 2,617,180 ኩ/ል ዩሪያ፣ 327,904 ኩ/ል ምርጥ ዘር፣ 313,015 ሊትር ፀረ አረም (2-4D)፣ 1,440 የዉሀ ሞተር፣1,220 ትርድል ፓምፕ፣ 120 ጠብታ፣1,750 የንብ ቀፎ ታቅዶ 1,284,170 ኩ/ል ዳፕ፣ 1,086,475 ኩ/ል ዩሪያ፣ 95,411 ኩ/ል ምርጥ ዘርና 27410 ሊትር ፀረ አረም፣ 807 የዉሀ ሞተር፣ 470 ትርድል ፓምፕና 1830 የንብ ቀፎዎች በኅብረት ሥራ ማኅበራት በኩል ለማቅረብ ተችሏል፡፡

## ለገበያ የቀረቡ ምርትና አገልግሎቶች

አባላት ላመረቱት ምርት የተሻለ ዋጋ እንዲያገኙና የተለያዩ ሸቀጣ ሸቀጦችን በተመጣጣኝ ዋጋ ማግኘት እንዲችሉ ለማድረግ 4,273,015 ኩ/ል የተለያዩ የሰብል ምርቶችን፣ 90,899,721 ሊትር ወተት፣ 64,946 የቁም እንስሳት፣ 1,250 የንብ ቀፎ፣ 112,016 ኩ/ል ማር፣ 72,381 ኩ/ል ዓሣ፣ 48338 ኪ/ግ ወርቅ፣ 807,632 ኪ/ግ ታንታለም፣ 31,000 ኩ/ል ዕጣን፣ 71,551,146 ብር የሚያወጣ ድንጋይና አሸዋ፣ 2,464,771,524 ብር የሚያወጡ ሸቀጣ ሸቀጦች ለገበያና ለአባላቱ ለማቅረብ ታቅዶ 127,626,679 ኩ/ል የተለያዩ የሰብል ምርቶች፣ 3765139 ሊትር ወተት፣ 643 የቁም እንስሳት፣ 1,250 የንብ ቀፎ፣ 994 ኩ/ል ማር፣ 2576 ኩ/ል ዓሣ፣ 5141 ኪ/ግ ወርቅ፣ 79259 ኪ/ግ ታንታለም፣ 18945 ኩ/ል ዕጣን፣ 9,980,627 ብር የሚያወጣ ድንጋይና አሸዋ፣ 311,546,094 ብር የሚያወጡ ሸቀጣ ሸቀጦች በኅብረት ሥራ ማኅበራት በኩል ለገበያና ለአባላቱ በማቅረብ ግብይቱ የተሳለጠ እንዲሆን ተደርጓል፡፡ በሌላ በኩል ደግሞ የግብይት ትስስሩ በመዋቅር የታገዘ ባይሆንም ልዩ ድጋፍ በሚሹ ክልሎች በእንስሳት ግብይት ትስስር እንዲፈጥሩ ሙያዊ ድጋፍ ተደርጓል፡፡ በመሆኑም የአገልግሎቱ ውጤታማነት ቀጣይ እንዲሆን ሊታሰብበት ይገባል፡፡

## በኅብረት ሥራ ማኅበራት ገበያ ለማረጋጋት

በምግብ ሸቀጥ አቅርቦትየተፈጠረውን ክፍተት ለመሙላት ማህበራት ጥረት አድረገዋል፡፡ በሦስት ክልሎች ብቻ 26335244 ሊትር የምግብ ዘይት 1012062 ኩ/ል ስኳር 341951 ኩ/ል የምግብ እህል 159572760 ቆን ሸቀጣሸቀጥ ከአምራችና ጅምላ ነጋዴዎች በመረከብ ለሕዝብ በዋጋው አከፋፍለዋል፡፡ የተቀሩትን ክልሎች በዚሁ ስሌት መገመት ይቻላል፡፡

ብር 345,947,720 በመሠረታዊ ማኅበራትና ብር 264,278,730 በዩኒየኖች ለመቆጠብ ታቅዶ ብር 75,020,063 በመሠረታዊ ማኅበራትና ብር 30,127,750 ደግሞ በዩኒየኖች ለመቆጠብ ተችሏል፡፡

ቁጠባውን ወደ ኢኮኖሚው ውስጥ አስገብቶ ልማት ለማምጣት ብድር ማመቻቸትና ማሰራጨት ሌላው ትልቅ ተግባር ነው፡፡ ስለሆነም ብር 75,600,000 ለመሠረታዊ ማኅበራትና ብር 4,615,960 ለዩኒየኖች የብድር አገልግሎት ለመስጠት ታቅዶ ብር 39,281,097 ለመሠረታዊ ማኅበራትና ብር 9,518,095 ለዩኒየኖች የብድር አገልግሎት ለመስጠት ተችሏል፡፡

ምንጭ፡- ፕላንና ፕሮጀክት ዳሬክቶሬት

ከሀምሌ 2004 እስከ መጋቢት 2005 ዓ/ም በህብረት ሥራ ማህበራት የቀረበ ሸቀጥ መጠን

| ሸቀጥዓይነት | መለኪያ | ደቡብ | አዲስ አበባ | አማራ | |
|---|---|---|---|---|---|
| የምግብ ዘይት | ሊትር | 2472208 | 23863036 | 0 | 26335244 |
| ስኳር | ኩ/ል | 263687 | 748375 | 0 | 1012062 |
| የምግብ እህል/ | ኩ/ል | 92281 | 249670 | 0 | 341951 |
| ሸቀጣሸቀጥ | ቆን | 3580 | 0 | 159569180 | 159572760 |

## የቁጠባ እና ብድር አገልግሎት

ከዕድገት ምንጮቻችን አንዱ ቁጠባ ነው፡፡ ባህሉን ለማሳደግ ደግሞ የገንዘብ ቁጠባና ብድር ኅብረት ሥራ ማኅበራት ጠንክረው በመስራት ላይ ናቸው፡፡ ባለፉት 9 ወራት ብቻ






ሕምበባያ የገንዘብ ቁጠባና ብድር ኅብረት ሥራ ማኅበር በሕፃናት ቁጠባ ቀን አባላት ሲያስተናግድ

# ለግንዛቤዎ

## ኤክሳይዝ ታክስ ምንድ ነው?

የኤክሳይዝ ታክስ ቀጥተኛ ያልሆነ የታክስ አይነት ነው። የኤክስሳይዝ ታክስ በአገር ውስጥ በሚመረቱና ከውጪ ወደ አገር ውስጥ በሚገቡ የተወሰኑ ምርቶች/ዕቃዎች/ ላይ የተጣለ የታክስ አይነት ነው።

የኤክሳይዝ ታክስ በቅንጦት እንዲሁም መሠረታዊ በመሆናቸው ምክንያት የገበያ ፍላጐታቸው በማይቀንስ ዕቃዎች ላይ እንዲሁም የህብረተሰቡን ጤንነት የሚጐዱ እና ማህበራዊ ችግር የሚያስከትሉ ዕቃዎችን አጠቃቀም ለመቀነስ ሲባል የተጣለ ታክስ ነው።

ታክሱም የሚጣለው በ19 ምድብ በተደለደሉ የተለያዩ ዕቃዎች፣ ከውጭ አገር ሲገቡ ወይም አገር ውስጥ ሲመረቱ የኤክሳይዝ ታክስ ይጣልባቸዋል።

የኤክሳይዝ ታክስ ማስከፈያ ልክ እና የስሌት መሠረት ቀጥሎ በቀረበው ሠንጠረዥ የተዘረዘሩት ዕቃዎች ወደ ሀገር ውስጥ ሲገቡ የዕቃው ዋጋ፣ የመድህን አርቦን፣ የማጓጓዣ ወጪ እና በዕቃው ላይ የሚከፈለው የጉምሩክ ቀረጥ ጠቅላላ ዋጋ በዕቃው ላይ የሚከፈለው የኤክሳይዝ ታክስ ስሌት መሠረት ይሆናል።

በአገር ውስጥ ለተመረቱት ዕቃዎች የማምረቻ ወጪው የኤክሳይዝ ታክስ ስሌት መሠረት ይሆናል። የማምረቻ ውጪ ማለት ለምርት ተግባር በቀጥታ የሚውሉ ጥሬ ዕቃዎችና የጉልበት ዋጋ፣ ቀጥተኛ ያልሆኑ ግብአቶች ወጪ እና ኦቨርሄድ ወጪ ሲሆን ለማምረቻ መሣሪያዎች የሚታሰበውን የእርጅና ቅናሽ አይጨምርም።

በአገር ውስጥ በፋብሪካ የተመረቱ እና በጨርቃ ጨርቅ የሚሰሩ ወይም የተዘጋጁ ልብሶች እና ተሸከርካሪዎች አገር ውስጥ ሲገጠሙ ሊከፈል የሚገባው የኤክሳይዝ ታክስ ማስላት ሲያስፈልግ ለእነዚህ ዕቃዎች ማምረቻ የዋሉ ግብዓቶች ወደ አገር ሲገቡ የተከፈለው የኤክሳይዝ ታክስ ተቀናሽ ይደረጋል።

የኤክሣይዝ ታክስ የክፍያ ጊዜ ወደ አገር ለሚገቡ ዕቃዎች አስመጪዎች ከጉምሩክ በሚያወጡበት ጊዜ ሲሆን በአገር ውስጥ ለተመረቱ ደግሞ ከተመረቱበት ቀን ጀምሮ በ30 ቀናት ውስጥ የኤክሳይዝ ታክስ ይከፈላል።

### ኤክሳይዝ ታክስ የማስታወቅ ግዴታ

በታክስ አዋጅ ቁጥር 307/95 አንቀጽ "8" ድንጋጌ መሠረት በታክስ ባለስልጣን በሚሰጠው ቅጽ ላይ መግለጫ ሞልቶ በየ30 ቀኑ ለታክስ ባለስልጣኑ ያቀርባል።

## በአዋጅ ቁጥር 307/95 የኤክሳይዝ ታክስ የሚጣልባቸው የምርት /ዕቃዎች/ ዓይነቶች

- ማናቸውም አይነት ስኳር /በአንኳር መልክ/ ሞላስስን ሳይጨምር ..........33%
- መጠጦች/ለስላሳ መጠጦች፣ ከፍራፍሬ ጭማቂዎች በስተቀር/ በዱቄት መልክ የተዘጋጁ ለስላሳ መጠጦች....40%
- በፋብሪካ የታሸገ /የሚመረት/ውሃ..........30%
- ማናቸው አልኮል ያላቸው መጠጦች ቢራ፣ እስታውት ማናቸውም የወይን ጠጅ መጠጦች እና ውስኪ ....50%
- ሌሎች አልኮል ያለባቸው መጠጦች............100%
- ማናቸውም ዓይነት ንፁህ አልኮል ..............75%
- ትምባሆና የትምባሆ ውጤቶች የትምባሆ ቅጠል...20%
- ሲጋሬት፣ ሲጋራ፣ ሲጋሪሎስ፣ የፒፓ ትምባሆ፣ሱረትና ሌሎች የትምባሆ ውጤቶች.....75%
- ጨው..........30%
- ነዳጅ ሱፐርቤንዚን፣ ተራ ቤንዚን ፔትሮል ጋዞልንና ለሎች የሞተር ስፒርት..........30%
- ሽቶዎች እና ቶይለት ወተርስ..........100%
- ጨርቃጨርቅ እና ከጨርቃ ጨርቅ የተሰ ዕቃዎች ከተፈጥሮ ሐር ናይለን ከሱፍ ከሹራብ መልክም ቢሆን የተሰሩ ጨርቃ ጨርቆች..........10%
- ከብር ከወርቅ ከሌሎች ነገሮች የተሰሩ ጌጣጌጦች..20%
- ለመኖሪያ ቤት አገልግሎት የሚሆኑ ሳህን ጠቢያ መኪናዎች..........80%
- ለመኖሪያ ቤት አገለግሎት የሚሆኑ የልብስ ማጠቢያ መኪናዎች..........30%
- የቪዲዮ ዴክ..........40%
- የቴሌቪዥን እና የቪዲዮ ካሜራዎች..........40%
- ተቀባይ ቴሌቪዥን፣ ከግራማፎን ከሬዲዮ ወይም ከድምፅ መቅረጫና ማሰሚያ ማሰሚያ ጋር የተጣመሩ ቢሆኑም ባይሆኑም..........10%

## ለመንገደኞች ማጓጓዣ የሚሆኑ ተሽከርካሪዎች

- እስከ 1800 ሲሲ..........30%
- ከ1300-1800 ሲሲ ..........60%
- 1800 ሲሲ በላይ ..........100%
- የወለል ምንጣፎች..........30%
- የአስቤስቶስና የአስቤስቶስ ውጤቶች..........20%
- የጠረጴዛ፣ የግድግዳ፣ የእጅ ሰዓቶች.......... 20%
- አሻንጉሊቶች እና መጫወቻዎች..........20%

መሆኑን መረዳት ይገባናል፡፡

ምንጭ- ከኢትዮጵያ ገቢዎችና ጉምሩክ ባለስልጣን የኮሙኒኬሽን ቡድን

# የኅብረት ሥራ ግብይት

ቅንብር በአበራ በቀለ



የግብርና ኅብረት ሥራ ማህበራት የምርት ውጤቶች
በኤግዚብሽን የቀረበ

ብይት ለኅብረት ሥራ ማህበራት ግዴታ ነው፡፡ ማስፈፀሚያ ወሰኑ በማቋቋሚያ አዋጅ ቁጥር 147/91 ዓ.ም ላይ በግልፅ ተደንግጓል፡፡ የአዋጁ መውጣት አስፈላጊነት ተመሳሳይ ፍላጐት ባላቸው ሰዎች መካከል በፈቃደኝነት ላይ የተመሰረተ ኅብረት በመፍጠር ገንዘብን ዕውቀትን፣ ንብረትንና ጉልበትን በማስተባበር ቁጠባንና ርስበርስ መደጋገፍን የሚፈጥሩ የኅብረት ሥራ ማኅበራትን ማቋቋም አስፈላጊ በመሆኑ እና እነዚህ ኅብረት ሥራ ማኅበራት በነፃ ገበያ የኢኮኖሚ ሥርዓት ውስጥ ተገቢውን ሚና እንዲጫወቱ ማድረግ በማስፈለጉ ነው፡፡

ግብይት ማህበራት የአባሎቻቸውን ገቢ በማሻሻል ማህበራዊና ኢኮኖሚያዊ ችግሮች የሚቀረፉበት እና ለስራ የሚሠማሩበት የሥራ ዘርፍ መሆኑን ማቋቋሚያ አዋጁ ይነግረናል፡፡ በዚህ አዋጅ መሠረት የህብረት ሥራ ማህበራት ብቁና ጠንካራ ተወዳዳሪ እንዲሆኑ በህግና ደንባቸው ላይ ተመስረተው የግብይት ቁመናና ስነምግባር አሟልተው ለአባሎቻቸው የግብዓት አቅርቦትና ምርት አሰባሰቦ፣ እሴት ጨምሮና ገበያ አፈላልጎ መሸጥና ሌሎች ተጓዳኝ የግብይት ሥራዎችን መሥራት እንደ አንድ አበይት ተግባር ግዳጅ ተጥሎባቸዋል ማለት ይቻላል፡፡

ይህ ተግባራቸውን ያለምንም እክል ተፈፃሚ እንዲያደርጉ ደግሞ በህብረት ሥራ አዋጅ ቁጥር 147/91 ዓ.ም ማሻሻያው ቁጥር 402/96 ዓ.ም በህጋዊ ግመንገድ የተመዘገበ ማንኛውም ህብረት ሥራ ማኅበር ከተመዘገበበት ቀን ጀምሮ ተጨማሪ ንግድ ፈቃድ ሳያስፈለገው በማንኛውም ንግድ ሥራ ላይ መሠማራት ይችላል በማለት የማያሻማ የሕግ ሽፋን ሰጥቷቸዋል፡፡

የአምስት ዓመቱ የዕድገትና ትራንስፎርሜሽን ዕቅድም በገጠር የግብርና ግብይት ሥርዓት ሲታሰብ ያለ አርሶ /አርብቶ አደሩ የህብረት ሥራ ማኅበራት ሠፊ ተሳትፎ መሠረታዊ ለውጥ ማምጣት አይቻልም ይላል፡፡

በሕጉ ወሰን ተደራጅተው በግብርናም ሆነ በሌሎች የማምረት ሥራ ላይ የሚሠማሩ የኅብረት ሥራ ተቋማት ለማምረት የሚያስፈልገውን ወጪና የአገልግሎት ዋጋን ለመቀነስ አባላት የሚፈልጉትን ግብዓት ወይም አገልገሎት በአነስተኛ ዋጋ እንዲያገኙ ምርታቸው ወይም አገልግሎታቸው የተሻለ የገበያ ዋጋ እንዲያገኝ የሚሠሩ በርካታ ኅብረት ሥራ ማኅበራቱ ተፈጥረዋል፡፡ ምርት ጥራቱ እንዲጠበቅ ከዘመን ዘመን እንዲዘልቅና እሴት እንዲጨምር የማቀናበር ሥራ ይሠራሉ፡፡ በፌደራል ደረጃ የግብይት መዋቅር ተፈቅዶ ፈፃሚ ባለሞያ ተሟልቶ የተደራጀ መረጃ ባይኖርም ከግብርና፣ ከንግድና ማዕድን ሚኒስቴር የተሰበሰበው መረጃ ትልቅ ማሳያ ይሆናል፡፡ በተለይ በግብርና ሥራ ዘርፍ የተሠማሩት ያስመዘገቡት ውጤት አበረታች ነው፡፡ ባስመዘገቡት የላቀ ተግባርም ተሸላሚ ሆነዋል፡፡ ድህነትን ለመርታት በተከፈተው ዘመቻ በርካታ አስተዋጽኦ እያበረከቱ ብዙም ያልተነገረላቸው ኅብረት ሥራ ማህበራት በንግድ ዘርፉ ያስገኙትን ውጤት መመልከት የተሻለ ነው፡፡



በ6ኛው ሀገር አቀፍ የርሶአደሮች ቀን በዓል ላይ የላቀ ውጤት ያስመዘገቡ ኅብረት ሥራ ማኅበራት ሲሸለሙ

## ዘመናዊ የግብርና ምርት ግብይትን ለማስፋፋት ኅብረት ሥራ ማኅበራት ያበረከቱት አስተዋጽኦ

የኅብረት ሥራ ማኅበራት የኢትዮጵያ ግብርና ምርት ገበያን ዘመናዊ ለማድረግ እየሠሩ ነው፡፡ ከኢትዮጵያ ምርት ገበያ በሚያዝያ 2005 ዓ.ም በተገኘው መረጃ ከአራት ትርፍ አምራች ክልሎች፤ ኦሮሚያ፣ አማራ፣ ትግራይና ደቡብ በሚገኙ 2 ፌደሬሽንና 13 ዩነየኖች 13,377 መሠረታዊ ማህበራት አባል በመሆን የ 1,901,752 አርሶ አደሮች ምርት ለውጭ ገበያ ደረጃውን ጠብቀው አደራጅተውና አቀናብረው ለገበያ በማቅረብ መንግስት ያደራጀውን ዘመናዊ የግብይት ስርአት እየደገፉ ናቸው፡፡ ዘመናዊነት የሥልጣኔ መገለጫ የግብርና ሽግግር ማረጋገጫ በመሆኑ ዩኒየኖች በምርት ገበያ ውስጥ መቀመጫ እንዲኖራቸው ለማድረግ በተደረገው ጥረት 30 ማኅበራት መቀመጫ እንዲኖራቸው መደረጉ በግብይቱ የማኅበራትና ሚናን ያመላክታል፡፡

## በወርቅ ግብይት የኅብረት ሥራ ማኅበራት ተሳትፎና የተመዘገበ ውጤት

ኢትዮጵያችን ከታደለችው ተስማሚ አየርና መልክዓምድር በተጨማሪ የተፈጥሮ በረከቷ የከበሩ ማዕድናት ናቸው፡፡ከብዙዎቹም አንዱ ወርቅ ነው፡፡ ሀብቱ ለአካባቢው ነዋሪ የኑሮው ዋስትናና ለሀገር ግንባታ ደግሞ የውጭ ምንዛሬ ምንጭ እየሆነ መጥቷል፡፡

ሀብቱን አልምቶ ዋጋ ለማስገኘት ከተሰማሩ አምራቾች በዋናነት ባህላዊ የወርቅ አምራች ኅብረት ሥራ ማኅበራት ይገኙበታል፡፡ ይባክን የነበረውን ሀብት ማኅበራቱ በማልማት ለብሔራዊ ባንክ ገቢ ያደርጋሉ፡፡ ባለፉት ጥቂት ዓመታት ባደረጉት ጥረት የተመዘገበው ውጤት ቀላል የሚባል አይደለም፡፡ ከ2003 እስከ 2005 ዓ.ም አጋማሽ ብቻ 15636751 ግራም ወርቅ አምርተው ለብሔራዊ ባንክ በማቅረብ 761720493 የአሜሪካ ዶላር ገቢ አስገኝተዋል፡፡

ለሀገራችን ዕድገትም የተመዘገበው የዘርፉ ልማት መጠናከር ይፈልጋል፡፡ የኅብረትሥራ ዘርፍም ጅማሮውን አጠናክሮ ሀብቱን ለጋራ የሀገራችን ዕድገት እንዲውል መስራት ይኖርበታል፡፡

በባህላዊ የወርቅ አምራች ኅብረት ሥራ ማኅበራት ለብሔራዊ ባንክ የቀረበው ወርቅ መጠንና የተገኘ ገቢ በአሜሪካ ዶላር

| Year | Gold per gram | In USD |
|---|---|---|
| 2003 | 7295570.09 | 322462158.8 |
| 2004 | 8334483.78 | 439257992.3 |
| 2005 | 6696.9749 | 341.545 |
| total | 15636750.84 | 761720492.6 |

ምንጭ፡- የማዕድን ማ...

## የግብዓት አቅርቦት በኅብት ሥራ ማኅበራት



## ለምርትና ምርታማነት ዕድገት የግብዓት አቅርቦት በኅብረት ሥራ ማኅበራት

የግብርና ምርትና ምርታማነት ለተከታታይ ዓመታት ዕድገት ማስመዝገቡ ይታወቃል:: ለዚህ ውጤት መገኘት አንዱ አስተዋፅኦ የግብዓት አቅርቦት በጊዜ በመጠንና በቦታው መፈፀም በመቻሉ ነው:: የማዳበሪያ አቅርቦትና ስርጭት በየዓመቱ ዕድገት አሳይቷል:: የማዳበሪያ አቅርቦትና ስርጭት መጠን በ1996 ዓ.ም ከነበረበት 322,942 ሜትሪክ ቶን ወይም 8 ከመቶ በ2004 ዓ.ም ወደ 635,343 ሜትሪክ ቶን 16 ከመቶ ከግማሽ በላይ አድጓል::

ይህንን የማያቋርጥ የግብዓት ፍላጎት ለማሟላት ከአርሶአደሩ ደጅ አንጉዘው ያደረሱት ኅብረት ስራ ማህበራት መሆናቸው አይካድም:: ስለዚህ ኅብረት ሥራ ማኅበራት ለግብርናው ዕድገት የነበራቸውን ድርሻ በዚሁ መጠን ማስላት ይቻላል::

### የኅብረት ሥራ ማኅበራ ውጭ ምንዛሬ ግኝት:

ባለፉት ሰባት ዓመታት ሰባት የቡና አምራች ገበሬዎች ኅብረት ሥራ ዩንየኖች 50110.15826 ቶን ቡና ለውጭ ገበያ በመላክ 259,737,271.6 የአሜሪካን ዶላር አስገኝተዋል::

ይህ ውጤት ማህበራት የአባላትን ችግር ከመፍታት ባሻገር ለሀገር ኢኮኖሚ ግንባታ እያበረከቱ ያሉትን አስተዋጽኦ ያሳያል::

### የቡና ህብረት ሥራ ዩንኖች ለዓለም ገበያ 199-2005 ዓ.ም ስምንተኛው ወር ድረስ የላኩት ቡና መጠን በኪሎ ግራምና ያስገኙት የውጭ ምንዛሪ በዶላር

| ላኪዩንየኖች | 1999 | | 2000 | | 2001 | | 2002 | | 2003 | | 2004 | | 2005 | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | ኪ/ግራም | ዶላር | ኪ/ግራም | ዶላር | ኪ/ግራም | ዶላር | ኪ/ግራም | ዶላር | ኪ/ግራም | ዶላር | ኪ/ግራም | ዶላር | ኪ/ግራም | ዶላር |
| ኦሮሚያ | 3192589 | 11323214 | 3654195 | 16492052 | 3896520 | 17150706 | 4600100 | 21304107 | 7327620 | 40940567 | 4311640 | 32172365 | 4229 | 25383 |
| ሲዳማ | 2764180 | 9503350 | 2764300 | 12286185 | 1863600 | 9125054 | 2858580 | 13631800 | 3714540 | 21238569 | 2572200 | 19948327 | 1114 | 7415 |
| ይርጋ ጨፌ | 860840 | 2833814 | 766620 | 3269271 | 402300 | 1984077 | 1110540 | 5627249 | 1208700 | 7469428 | 815760 | 6667951 | 654 | 4806 |
| ከፋ | 150060 | 354335 | 89640 | 281869.6 | 72000 | 252748.7 | 144000 | 524217.3 | 206700 | 885820 | 128160 | 879033.5 | 121 | 621.1 |
| በቤንችማጂ | 0 | 0 | 18000 | 107140 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 108 | 302.4 |
| ሊሙኢናሪያ | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 321600 | 1495407 | 267000 | 1820769 | 269 | 1136 |
| ቴፒ | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 6300 | 29861.31 | 15360 | 98201.7 | 0 | 0 |
| ዳሞታ ወላይታ | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 0 | 19.2 | 118.5 |
| ድምር | 6967669 | 24014714 | 7292755 | 32436517 | 6234420 | 28512587 | 8713220 | 41087373 | 12785460 | 72059651 | 8110120 | 61586647 | 6514 | 39782 |

# የኅብረት ሥራ ማህበራት እውነታዎች

ቅንብር ይግዛው ዳኘው

## የመሠረታዊ ኅብረት ሥራ ማኅበራት ማስፋፋት

በዘርፉ በፌደራልና በየደረጃው የሚገኙ የኅብረት ሥራ ማኅበራት ማስፋፊያ አካላት በተደረገው ጥረት በርካታ ኅብረት ሥራ ማኅበራትን መልሶ የማቋቋም የማደራጀትና የማጠናከር ሥራዎች ተሰርተዋል፡፡ በዚህም በአገር አቀፍ ደረጃ ከ6.5 ሚሊዩን በላይ አባላትን ያቀፈና ከብር1.5 ቢሊዩን በላይ ካፒታል ያላቸው ከ43 ሺ በላይ መሠረታዊ ኅብረት ሥራ ማኅበራት ተቋቁመው በመንቀሳቀስ ላይ ይገኛሉ፡፡

## የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች ማስፋፋት

የመጀመሪያ ደረጃ ኅብረት ሥራ ማህበራት ሊፈቷቸው ያልቻሏቸውን ችግሮች በጋራ ለመፍታት የሚያከናውኗቸውን ተግባራት ጥራት ጠብቀው በነፃው የገበያ ኢኮኖሚ የመወዳደር አቅማቸውን በማሳደግና የተሻለ የአመራርና የአሠራር ሥርዓት ለመፍጠር የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች አስፈላጊ መሆኑን በመረዳት የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች የማደራጀት ጥረቶች እየተደረጉ ነው፡፡ በዚህም በአገር አቀፍ ደረጃ እስከ መጋቢት 30/2005 በተሰበሰበው መረጃ መሠረት ከ 8411 በላይ አባል ማኅበራትን ያቀፉ ከ 293 በላየ የኅብረት ሥራ ማኅበራት ዩኒየኖች ተቋቁመው ከብር1,504,535,524 ሚሊዮን በላይ ካፒታል በማንቀሳቀስ ላይ ይገኛሉ፡፡ የተሰማሩባቸው የሥራ መስኮችም፤ በሁለገብ፣ በሰብል ምርት ግብይት፣ በገ/ቁጠባና ብድር፣ በወተትና ወተት ተዋፅኦ፣ በቡና ግብይት፣ በደን ልማትና ጥበቃ፣ በአትክልትና ፍራፍሬ ልማት፣ በማዕድን፣ በሸንኮራ አገዳ ልማት፣ በንብ ውጤቶች ልማት፣ በምግብ ዝግጅትና በኮብል ንጣፍ ድንጋይ ሲሆን የአባላትንና የአካባቢውን ኅብረተሰብ ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ ችግሮች በመፍታት ለሀገር የኢኮኖሚ ዕድገት ዓይነተኛ አስተዋፅኦ እያበረከቱ ነው፡፡ ዝርዝራቸውም በሚከተለው ሠንጠረዥ ቀርቧል፡፡

## በሀገር አቀፍ ደረጃ የተቋቋሙ የኅብረት ሥራ ዩኒየኖች እስከ መጋቢት30/2005ዓ.ም.

| ተ.ቁ | የዩኒየኑ አይነት | አማራ | ኦሮሚያ | ደቡብ | ትግራይ | አ/አበባ | ቤ/ጉሙዝ | ድሬዳዋ | ሐረሪ | ድምር |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1 | ሁለገብ የገበሬዎች | | | | | | | | | |
| | ብዛት | 23 | 52 | 19 | 33 | | 10 | 1 | 1 | 139 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | **787** | 2100 | 497 | 509 | | 93 | 38 | 7 | 4031 |
| | ካፒታል | **156100475** | 480630228 | 41959536.19 | 56832567 | | 13231932 | 2291831 | 382000 | 751428569.2 |
| 2 | የወተት ልማትና ግብይት | | | | | | | | | |
| | ብዛት | 2 | 4 | | | | | | | 6 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | 12 | 51 | | | | | | | 63 |
| | ካፒታል | 937356 | 3197153 | | | | | | | 4134509 |
| 3 | የንብ ዉጤቶች | | | | | | | | | |
| | ብዛት | 1 | 1 | 1 | | | | | | 3 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | 9 | 12 | 12 | | | | | | 33 |
| | ካፒታል | 133126 | 24685.52 | 24685.52 | | | | | | 182497.04 |
| 4 | የገንዘብ ቁጠባና ብድር | | | | | | | | | |
| | ብዛት | 19 | 24 | 18 | 9 | 2 | 3 | 1 | | 76 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | 778 | 656 | 402 | 256 | 266 | 41 | 43 | | 2442 |
| | ካፒታል | 20817066 | 297617719 | 10562340 | 13128085.36 | 4820135 | 950000 | 516000 | | 348411345 |
| 5 | የደረቅ ምግብ ዝግጅት | | | | | | | | | |
| | ብዛት | | | | | 2 | | | | 2 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | | | | 30 | | | | 30 |
| | ካፒታል | | | | | 945443 | | | | 945443 |
| 6 | የሰብል ግብይት | አማራ | ኦሮሚያ | ደቡብ | ትግራይ | አ/አበባ | ቤ/ጉሙዝ | ድሬዳዋ | ሐረሪ | ድምር |
| | ብዛት | | 3 | | | | 2 | | | 5 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | 73 | | | | 8 | | | 81 |
| | ካፒታል | | 4644677 | | | | 727000 | | | 5371677 |
| 7 | ቡና | | | | | | | | | |
| | ብዛት | | 7 | 5 | | | | | | 12 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | 426 | 137 | | | | | | 563 |
| | ካፒታል | | 165384591 | 110992630.5 | | | | | | 276377221.50 |
| 8 | ደን | | | | | | | | | |
| | ብዛት | | 2 | | | | | | | 2 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | 16 | | | | | | | 16 |
| | ካፒታል | | 438727 | | | | | | | 438727 |
| 9 | የእንስሳት ግብይት | | | | | | | | | |
| | ብዛት | | 3 | 1 | | | | | | 4 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | 25 | 11 | | | | | | 36 |

| | | አማራ | ኦሮሚያ | ደቡብ | ትግራይ | አ/አበባ | ቤ/ጉሙዝ | ድሬዳዋ | ሐረሪ | ድምር |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | ካፒታል | | 1920687 | 900999 | | | | | | 2821686 |
| 10 | ሽንኩራ አገዳ | | | | | | | | | |
| | ብዛት | | 1 | | | | | | | 1 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | 7 | | | | | | | 7 |
| | ካፒታል | | 8771550 | | | | | | | 8771550 |
| | | አማራ | ኦሮሚያ | ደቡብ | ትግራይ | አ/አበባ | ቤ/ጉሙዝ | ድሬዳዋ | ሐረሪ | ድምር |
| 11 | ማዕድን | | | | | | | | | |
| | ብዛት | | 7 | | | | | | | 7 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | 386 | | | | | | | 386 |
| | ካፒታል | | 755252 | | | | | | | 755252 |
| 12 | አትክልትና ፍራፍሬ | | | | | | | | | |
| | ብዛት | 2 | 4 | 1 | | | 1 | | | 8 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | 31 | 118 | 15 | | | 17 | | | 181 |
| | ካፒታል | 380000 | 10042745 | 73380.25 | | | 2003901.82 | | | 12500027 |
| 13 | የሸማቾች | አማራ | ኦሮሚያ | ደቡብ | ትግራይ | አ/አበባ | ቤ/ጉሙዝ | ድሬዳዋ | ሐረሪ | ድምር |
| | ብዛት | 2 | 2 | 3 | 1 | 10 | 1 | | 1 | 20 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | 21 | 25 | 254 | 4 | 115 | 6 | | 7 | 432 |
| | ካፒታል | **1537595** | 601400 | 8772273.28 | 535623.1 | 7,867,619.7 | 300000 | | 3000000 | 22614511.38 |
| 14 | የዓሣ አስጋሪዎች | | | | | | | | | |
| | ብዛት | | 1 | | | | | | | 1 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | 10 | | | | | | | 10 |
| | ካፒታል | | 50000 | | | | | | | 50000 |
| 15 | ኮንስትራክሽን | | | | | | | | | |
| | ብዛት | | | | 1 | | | 1 | | 2 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | | | 21 | | | 23 | | 44 |
| | ካፒታል | | | | 160000 | | | 1100000 | | 1260000 |
| 16 | ዘርብዜት | አማራ | ኦሮሚያ | ደቡብ | ትግራይ | አ/አበባ | ቤ/ጉሙዝ | ድሬዳዋ | ሐረሪ | ድምር |
| | ብዛት | | 1 | 2 | | | | | | 3 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | | 24 | 31 | | | | | | 55 |
| | ካፒታል | | 142165 | 2206450.43 | | | | | | 2348615.43 |
| 17 | መስኖልማት | አማራ | ኦሮሚያ | ደቡብ | ትግራይ | አ/አበባ | ቤ/ጉሙዝ | ድሬዳዋ | ሐረሪ | ድምር |
| | ብዛት | 1 | 2 | | | | | | | 3 |
| | አ/ማህበራት ብዛት | 12 | 21 | | | | | | | 33 |
| | ካፒታል | 433500 | 1492924 | | | | | | | 1492924 |
| | ድምር | አማራ | ኦሮሚያ | ደቡብ | ትግራይ | አ/አበባ | ቤ/ጉሙዝ | ድሬዳዋ | ሐረሪ | ድምር |
| | ዩንየን | 50 | 113 | 50 | 44 | 14 | 17 | 3 | 2 | 298 |
| | አባል/ማኅበራት | 1650 | 3938 | 1359 | 790 | 401 | 155 | 104 | 14 | 8411 |
| | ካፒታል | **244,561,273** | **975,689,818** | 175,492,295.2 | 70656275 | 13633197.70 | 17212833.82 | 3907831 | 338000 | 1,504,535,524 |

